# ገድለ ቂርቆስ ወኢየሉጣ



ውዳሴ ወግናይ፣ መጽሐፈ ገድል፣
መጽሐፈ ተአምር፣
መልክአ ቂርቆስ፣ መልክአ ኢየሉጣ
በግዕዝና በአማርኛ

ተርጓሚ - መምህር ኅሩይ ኤርምያስ

ጥር ፲፱፻፺፯ ዓ.ም
አዲስ አበባ

# ገድለ ቂርቆስ ወኢየሉጣ

ውዳሴ ወግናይ፣ መጽሐፈ ገድል፣
መጽሐፈ ተአምር፣
መልክአ ቂርቆስ፣ መልክአ ኢየሉጣ
በግዕዝና በአማርኛ

ተርጓሚ -- መምህር ኀሩይ ኤርምያስ

ጥር ፲፱፻፺፯ ዓ.ም
አዲስ አበባ

የዚህ መጽሐፍ ሥርጭት ገቢና
መልሶ የማሳተም መብት ለመ/ስ/
ቅዱስ ቂርቆስ ቤ/ክ ሰ/ጉ/ጽ/ቤት
ተሠጥቷል።

መጀመሪያ እትም 1997 ዓ.ም.



ብፁዕ ወቅዱስ አቡነ ጳውሎስ ፓትርያርክ
ርእሰ ሊቃነጳጳሳት ዘኢትዮጵያ ሊቀጳጳስ ዘአክሱም
ወእጨጌ ዘመንበረ ተክለሃይማኖት
(በሆኑ፡ ፲፩ኛ ዓመት ታተመ)

# መግቢያ

በስመ አብ ወወልድ ወመንፈስቅዱስ አሐዱ አምላክ አሜን፡፡

ቅድስና በጥበብ ወይም በገንዘብ አልያም በውርስ ከሰው የሚያገኙት ምድራዊ ሀብት ሳይሆን የሚያይቱን ዓለም በማያዩት ዓለም ለውጦ የዓለምን መከራ ታግሦ ፍጹም እግዚአብሔርን መስሎ በመኖር ከአምላክ የሚገኝ ሰማያዊ ጸጋ መንፈሳዊ ክብር ነው፡፡

ቅዱሳን ከተባሉት መካከል የፈተና መድረክ በሆነችው ዓለማችን ዳዋ ጥሶ ጤዛ ልሶ ደንጊያ ተንተርሶ ዘመኑን ዘመን ሳይለው በተኅርምት ሳይኖር ሥጋውን ከዓለም ተድላ ደስታ ሳይለይ፤ ስለራሱና ስለ ሕዝቡ ኃጢአት ሳያዝን ሳያለቅስ፤ ስሙን በካዱ በዐላውያን አደባባይ የእግዚአብሔርን አምላክነት ለመመስከር አንገቱን ለስለት አካሉን ለእሳት ሳይሰጥ፤ ሰውነቱን በጾም በጸሎት በሰጊድ ሳይቀጣ፤ በብዙ ጭንቅና መከራ ውስጥ ሳያልፍ ቅዱስ የሆነ ወይም የተባለ አንድ እንኳ የለም፡፡ ነቢያት ሐዋርያት ጻድቃን ሰማዕታት እኒህ ሁሉ በመጋዝ እስኪተረተሩ በደንጊያ እስኪወገሩ ለአራዊት እስኪጣሉ በግንድ እስኪሰቀሉ ድረስ በመከራ ውስጥ አልፈው በሞታቸው ፈጣሪያቸውን ያገለገሉ ታማኝ ባለሟሎች ናቸው፡፡ ዕብ 11:35-38

በዚህ መጽሐፍ ዜና ገድላቸው የተጻፈላቸው እናትና ልጅ ቅድስት ኢየሉጣና ቅዱስ ቂርቆስም በሞታቸው ፈጣሪያቸውን አገለገሉ ካልናቸው ሰማዕታት መካከል ከፊተኞቹ ጋር የሚጠቀሱ ናቸው፡፡

ዘመኑ ልዑል እግዚአብሔርን ማመን ማምለክ እንደ ነውር ክፉ መቅሠፍትንም እንደሚያስከትል ስህተትና ድፍረት ተቆጥሮ ምእመናን እንደ በግ የሚታረዱበት በእሳት የሚቃጠሉበት በመንኰራኩር የሚፈጩበት የጌታ ኃይል ተዘንግቶ ዲያብሎስ የነገሠበት የጭንቅና የመከራ ዘመን ነበር፡፡ ዲያብሎስ ከመጀመሪያው ሰው ከአዳም ጀምሮ የእግዚአብሔር የሆኑትን ከማሳደድ የቦዘነቡት ጊዜ ባይኖርም በተለይ ዘመነ ሰማዕታት ተብሎ በሚታወቀው በዚያ ዘመን /3ኛው መቶ ክ/ዘ 2ኛ አጋማሽ/ በቤተክርስቲያንና በምእመናን ላይ ያደረሰው ጥፋት ግን በየትኛው ም ክፍለ ጊዜ ካደረገው እጅግ የከፋ ነበር፡፡ በመስቀልና ሐዋርያት ከዓለም ዳርቻ እስከ ዓለም ዳርቻ ድረስ ዞረው የምሥራቹን ቃል ሲነግሩ በቃላቸው ትምህርት በእጃቸው ተአምራት አሕዛብ ከአምልኮ ጣዖት ወደ አምልኮ እግዚአብሔር ከገቢረ ኃጢአት ወደ ገቢረ ጽድቅ በመመለሳቸው ምክንያት ያደረሰበትን ታላቅ ሽንፈት ሊያካክስ ወዳጆቹ ዐላውያን ነገሥታት መኳንንት ሁሉ እጆቻቸውን በምእመናን ላይ እንዲጭኑ አደረገ፡፡ አብያተ ክርስቲናት ተቃጠሉ መጻሕፍት ተቈነጸሉ፣ ጣዖት አናመልክም ያሉት ሁሉ በግፍ ተገደሉ ሽንፈቱ ግን አሁንም የርሱ ነበር፡፡ ሰማዕታቱ ጌታ አስቀድሞ

«ወኩን መሀይምነ እስከ ለሞት ወእሁበከ አክሊለ ሕይወት= እስከሞት ድረስ የታመንህ ሁን የሕይወትንም አክሊል እሰጥሀለሁ» ራእ ፪፡፲ ብሎ ክርስትና እሾህ ጋሬጣውን አልፈው መልካሙንና ጣፋጩን ፍሬ የሚቀምሱባት በእሾህ የታጠረች ተክል መሆኗን ለወዳጆቹ የገለጠበትን አምላካዊ ቃል በመጠበቃቸው በምድራዊው ፈንታ ሰማያዊውን በጊዜያዊው ፈንታ ዘላለማዊውን ክብር ተቀብለዋል የሕይወትንም አክሊል ተቀዳጅተዋልና።

በዚህ ጊዜ ነበር እንግዲህ እኒህ ሁለቱ ቅዱሳን እናትና ልጅ መከራውን ሳይሰቀቁ የጣዖትን ከንቱነት የልዑል እግዚአብሔርን አምላክነት መስክረው የሰማዕትንትን ክብር የተጐናጸፉት።

የገድላቸው መጽሐፍ የሃይማኖታቸውን መሠረትና ጽናት፣ የጣዖትን ከንቱነት፣ የመላእክትን ተራዳኢነት የልዑል እግዚአብሔርን አዳኝነት ይነግረናል። የ3 ዓመት ሕጻን በርቱዕ አንደበት የጌታን አምላክነት በአደባበይ መመስከሩ፤ እናቱን መምከር ማስተማሩ፤ ሲሰሙት እንኳ የሚ ገድለውን አስደንጋጭ መከራ መታገሡ ሃይማኖት ለጐደላቸው የእምነት ድሆች ለማመን የሚያዳግት ሊሆን ይችላል። «እስመ አልቦ ዘይሰአኖ ለእግዚአብሔር» ሉቃ ፩፡፴፯ ያለውን ይዘን ጌታ ሁሉን ማድረግ እንደሚችል የሚሳነውም ምንም ምን እንደሌለ የምናምን ኦርቶዶክሳውያን ግን ጌታ በሕጻኑ ያደረገውን ድንቅ የበለዓምን አህያ በሰው አንደበት ከማናገሩ ዘኁ ፳፪፡፳፰ የሚጠቡት ሕጻናትና የቢታንያ ደንጊያዎች ሆሣዕና በአርያም ቡሩክ ዘይመጽእ በስመእግዚአብሔር ብለው እንዲያመሰግኑት ከማድረጉ ሉቃ ፲፱፡፵ ብላቴናው ዳዊት አርበኛው ጐልያድን ደካማይቱ ዮዲት ብርቱውን ሆሎፎርኒስን እንዲያቸንፉ ፩ ሳሙ ፲፯፡፶ ዮዲ ፲፬፡፲፩ ከማስቻሉ ጋር አንድ አድርገን በመቁጠር በርግጥም ሐዋርያት እስመ በብዙኅ ሕማም ሀለወነ ንባእ ለመንግሥተ እግዚአብሔር ሐዋ ፲፬፡፳፪ እንዳሉ መንግሥተሰማያት በብዙ ጭንቅ (ምግባር ትሩፋት) የሚገባባት እንጂ ሆዴ ይሙላ ደረቴ ይቅላ ብሎ ስለሥጋ በማሰብና በዋዛ በፈዛዛ የማትገኝ መሆኗን፤ ስለእግዚአብሔር ብለን የተቀበልነው መከራ ሰማያዊ ዋጋ እንደሚያስጠን ተረ ድተን ሕይወታችንን የምንፈትሽበት ራሳችንን የምናንጽበት እውነታ ነው።

መጽሐፉ ከመጽሐፍቅዱሳዊ ታሪኮችና ኃይል ቃሎች ጋር እየተነጻጸረ የተጻፈና በሚረዳ ሁኔታ የተተረጐመ መጽሐፋዊ ማስረጃዎችንም የያዘ በመሆኑ ከሌሎች መሰል መጻሕፍት ለየት ያለ ነው። ሰማዕቱ ከአምላኩ በተቀበለው ቃል ኪዳን ሰውን የሚያማልድ ክብርን ፈውስን የሚያስጥ መሆኑን ኢትዮጵያውያን በተለየ ሁኔታ እንረዳዋለን። በመሆኑም ዜናውን አንብበን ልንማርበት የጸሎቱንም ክፍል ጸልየን ልንጠቀምበት ይገባል።

ወስብሐት ለእግዚአብሔር

# ክፍል ፩

## ምዕራፍ ፩

## ውዳሴ መግናይ

፩ በእግዚአብሐር አብ ስም ይቅር ባይ ከቁጣ የራቀ ምሕረቱም የበዛ በደልና ኃጢአትን የሚያቃልል በአካል ሦስት በመለኮት አንድ የሚሆን በሰውና በመላእክት በፍጥረትም ሁሉ እንደበት በምድርና በሰማያት በባሕርና በቀላያት ምስጋና ለርሱ ይሁን ለዘላለሙ አሜን ዘጸ ፴፬ : ፯

፪ ተቀዳሚ ተከታይ በሌለው በእግዚአብሔር ወልድ ስም ይቅር ባይ ከቁጣ የራቀ ሰማይን እንደ ጠፈር የዘረጋ ምድርንም በጥልቅ ባሕር ላይ የሠራት ውኆችን እንደ ድንኳን ያቆመ በሥራው የተገለጠ በባሕርዩ ግን የረቀቀ ጻድቅ በሩቅና በቅርብ በታችና በላይ ያለው ፍጥረት ሁሉ ፈጣሪ እርሱ ነው:: የምስጋና ስሙ ከምዕራብ እስከ ምሥራቅ የተመሰገነ ይሁን በሽማግሌዎችና በልጆች እንደበት ለርሱ ምስጋና ይሁን ለዘላለሙ አሜን ዮሐ ፲:፲፰

፫ በእግዚአብሔር መንፈስ ቅዱስ ስም ከአብና ከወልድ የማይለይ በአገዛዝና በልዕልና የሚተካከል ከሰማየ ሰማያት ከፍ የሚል ከቀላየ ቀላያት ጥልቅ የሚሆን በኅሊና ፍለጋ የማይገኝ በዓይነ ኅሊና የማይታይ ከሦስቱ አካላት አንዱ መሆኑን የማያምን ኃጢአተኛ በደለኛም ሰው የሥቃይ ቦታ ወደሚሆን የገሃነም ጥልቅ ይውረድ ለርሱ ምስጋናና ታላቀነት ውዳሴና መገዛት በታላቁም በታናሹም እንደበት ይሁን ለዘላለሙ አሜን ማቴ ፲፪:፴፪

፬ አቤቱ የእግዚአብሔር አብ የባሕርይ ልጅ የምእመናን መመኪያ የሆነች የድንግል ማርያምም ልጅ ጌታዬ ኢየሱስ ክርስቶስ ሆይ ርዳኝ፣ አቤቱ የሰው እንደበት ሊፈጽመው ከማይችለው በጆሮ ለሚሰማው ድንቅ ከሆነ ነገርን ከጉረሮ ከሚለይ ከእህልም ይልቅ ከሚጣፍጥ ደስ ካለው ከዚህ ሕጻን ገድሎች ጥቂት እንድናገር የጥበብ ከንፈሮችን የአንደበትንም መጣፈጥ ስጠኝ:: ለዓለም ሁሉ ከሚያበራ ብርሃን የተገኘህ ብርሃን እኛን ስለማዳን በዓለም ላሉም የተሠወረውን ምሥጢር ትገልጥ ዘንድ በዓለም የተገለጥህ ሆይ ንዑድ ክቡር ከሚሆን ምስክርህ ከሕጻን ቂርቆስ ከድንቆቹ ኋላ እንድከተል የልቤን ደጃፍ የጋረደውን የድካም መሸፈኛ ግለጥ:: ገድሎቹን ወደ መናገር እስክደርስ በምስጋናህ ብርሃን ጉዳና ያለጥርጥር ወደ አንተ እለምናለሁ ዲዳዎችን ስለአንተ ያስተምሩ ዘንድ ያደረግሀቸው ሆይ ሰሚዎች ደስ ያለው የንዑድ ክቡር ሕጻን ቂርቆስን ገድሉን ለመስማት ይመራሩ ዘንድ ዕውቀትን ላጣሁ ለእኔ የኀቡዓትህን መንፈስ በኅሊናዬ እናግር አሜን::

፭ አሁንም አቤቱ ምስክሬ ሕጻን ቂርቆስን የፈለገውን እኔ እረዳዋለሁ ረዳትና መንገድ መሪም እሆነዋለሁ በል ሁሉን የፈጠርህ የዓለምም ሁሉ መሠረት ሆይ ሁሉን ለሕይወታችን በጥበብህ የፈጠርህ በምሥጢሮችህም የእግዚአብሔር ልጆች እንድንሆን አዲሶች አደረግኸን /አደስከን/::

፮ ሁሉን በሚያቸንፍ ታላቅ ኃይልህ አቤቱ በባለሟሎችህ ላይ ክፉን ቃል እንዳይናገር የበደለኛውን አፉን ዝጋ ኅሊናውንም የዕውቀት ሀገር ወደ ሆነ ሀገርህ አሳርግ ይህን የሚያልፍ ዓለም እንደናቁ የሰማይንም ሠርግ እንደመረጡ ቅዱሳን እስከመጨረሻው ሕቅታ ድረስ ያለመለየት ከጽልና ከጠብ መንገድ ይርቅ ዘንድ በልቡ ሰላምና ፍቅርን ሙላ::

፯ ልብን ከፈጣሪዋ መንገድ ከምታስታት የዓለም ፍላጐት አፉን የሚከለክል ንዑድና ክቡር ነው፣ የብርሃን ሠራዊት ከሚመገቡት የልዑል ማዕድ ይበላልና::

፰ ምግቡ ከእርሱ ለሚበሉ ፍጡራን ሁሉ በአዲስ ዓለም ሕይወትን የሚሰጥ ከላይም የወረደ ከሚሆን ከዚያ ኅብስት የሆነ ንዑድ ክቡር ነው::

፱ ከጣዕሙ የተነሣ ልቡን ደስ እንዲለው ከአብ እቅፍ የፈሰሰውን የሕይወት መጠጥ የጠጣ ንዑድ ክቡር ነው::

፲ የተናቁ የፍትወታት እድፎችን የሚሸከም ያይደለ የክርስቶስ ፍቅር በአጥንቶቹ ያደረ ንዑድ ክቡር ነው::

፲፩ የዚህን ዓለም ወዳጆች የሚወድ ያይደለ ለመላእክት ጓደኛ የሆነ ንዑድ ክብር ነው::

፲፪ በዚህ ዓለም ውበት ያይደለ የሁሉን ጌታ ውበት በማየት ኅሊናው የተማረከ ሰው ንዑድ ክቡር ነው::

፲፫ በኅሊና ትጋት የሚታሠር ያይደለ ልቡ በእግዚአብሔር እርሱንም በማሰብ የሚታሰር ንዑድ ክቡር ነው::

፲፬ እግዚአብሔርን የሚያገኘው ዐዋቂም የሚሆነው ንዑድ ክቡር ነው:: ኅሊናው ከላይኛው ዓለም አይወርድምና::

፲፭ በጸሎት ባሕር የሚዋኝ ንዐድ ክቡር ነው ለራሱ ዕንቁዎችን ይመርጣል ያበሩና ያምሩም ዘንድ በልዕልና ባሕር ያጥባቸዋል::

፲፮ በመንፈስቅዱስ ክንፎች እየበረረ ወደብርሃን ማደሪያዎች የሚሄድ ንዑድ ክቡር ነው፡፡

፲፯ የተገኘባት ምድርን የናቃት በዓለም ሁሉ ምንጭ እቅፍም ይጠመቅ ዘንድ የተገባው ንዑድ ክቡር ነው፡፡

፲፰ የግዮን ውኃን መጠጥ የናቀ ነፍሱንም በጊዜው ሁሉ ከሕይወት ውኃ የሚያረካት ንዑድ ክቡር ነው፣ የዓለም ብርሃን ከሚሆን የክብር ምንጭ ኢየሱስ ክርስቶስ የሚጠጡ አይሞቱምና፡፡

፲፱ ዓለምህ ፈጣሪህ ሀብትህም በመንፈስ መኖር ምግብህም ውበቱን ማየት መጠጥህም በነፍስ ውስጥ ያለው የመንፈስ ሥራ ነውና ሕጻን ቂርቆስ ሆይ ክብር ይገባሀል፡፡

፳ ፀሐይህ አይገባም የዓይኖችህም ሽፋሽፍቶች የሌሊትን ጨለማ አያዩምና ደስ ያለህ ሕያው ሕጻን ቂርቆስ ሆይ ክብር ለአንተ ይገባል፡፡

፳፩ ውበትህ አይጠወልግም በመድኃኒታችን በክርስቶስ ብርሃንም ያበራልና የክርስቶስ ሰማዕት ሆይ ክብር ለአንተ ይገባል፡፡

፳፪ ደስታህ በእግዚአብሔር ነውና ለዘላለም ከነፍስህ ውስጥ አይጠፋምና ቂርቆስ ሆይ ንዑድ ክቡር ነህ፡፡

፳፫ በምድር ሳለህ ከእሷ ተለይተሀልና ነፍስህም ከመንፈሳውያን ጋር በደስታ ትዞራለችና ቂርቆስ ሆይ ንዑድ ክቡር ነህ፡፡

፳፬ የሚጠፋውን ምግብ ንቀህ ከእርሱ ጋር ስትነጋገር ልብህ በጌታህ በእግዚአብሔር ጣዕም ተመልታለችና ቂርቆስ ሆይ ንዑድ ክቡር ነህ፡፡

፳፭ ቂርቆስ ሆይ ንዑድ ክቡር ነህ ዳግመኛም ያለድካም በአርምሞ ሁሉ ለሚደረግልህ ለአንተ ክብር ይገባል፡፡ ማቴ ፳፩፡፳፩-፳፪

፳፮ ቂርቆስ ሆይ ክብር ይገባሀል በነፍስህ ውስጥ የሕይወት መዝገብን ገዝተሀልና ይኸውም በወዳጆች ዘንድ የሚገለጥ ክርስቶስ ነው፡፡ ሀብት ሁሉ የእርሱ ነውና፡፡ መዝ ፵፱፡፲፪

፳፫ የእግዚአብሔር ሕግ ፈቃድህ የሆነ ሕጉንም በቀንና በሌሊት የምትናገር እንጂ በዝንጉዎች ምክር ያልሄድህ በኃጥአንም መንገድ ያልቆምህ በዘባቾች መቀመጫም ያልተቀመጥህ ቂርቆስ ሆይ አንተ ንዑድ ክቡር ነህ፡፡ ጥበብ የዲዳዎችን አፍ ከፈተች የሕጻናትንም አንደበት የቀናውን ነገር የሚናገር አደረገች / / ያለው የጠቢቡ ቃል በእውነት በአንተ ላይ ተፈጸመ፡፡ ነቢዩ ኢሳይያስ ሕጻኑ አባቱንና እናቱን መጥራት ሳያውቅ የደማስቆን ሀብትና የሰማርያን ምርኮ በፋርስ ንጉሥ ፊት ይካፈላል /ኢሳ ፰፡፬/ እንዳለ አበ እመ ማለትን ሳታውቅ ኃይልና ጽናትን በገድል ውስጥ ይዘህልና በእውነት በፋርስ ንጉሥ ከተመሰለ የአሕዛብ ነገሥታት አለቃ ከዲያብሎስ ብዙ ምርኮን ነጠቅህ ይኸውም የምእመናን ነፍስ ነው፡፡

፳፰ እግዚአብሔር ከእናትህ ማኅፀን የጠበቀህ ቂርቆስ ሆይ ንዑድ ክቡር ነህ ባለመልካም መዝሙር ዳዊት እግዚአብሔር ሕጻናትን ይጠብቃል /መዝ፻፲፬፡፪/ እንዳለ በእውነት ከጠላት ወጠመድ ጠበቀህ፣ አንተ ሕጻን ስትሆን በኃይልህ ብርቱ ሆነህልና፡፡

፳፱ መንፈሳዊ አርበኛ ቂርቆስ ሆይ ንዑድ ክቡር ነህ፣ የእርሻህን ትልም አዘንብለህ ወደኋላህ አልተመለስህምና በጠላት ፍላጻ ብትንደፍ እንኳ ሩጫዎችህን የሚጠብቅ መልአክ አለልህ ይኸውም ቁስልህን የሚፈውስና የመድኃኒት ቅባትን የሚቀባህ ሕዋሳቶችህንም ከጽኑ ድካም የሚያሳርፍ ነው፡፡ ከመከራ ጽናት የተነሣ የአፍአዊ ዓይንህ ብርሃን ቢጨልም የሁሉ ፈጣሪ ብርሃን የሆነላትን ሀገር አገኘሁት ሰማያዊ ሙሽራ የሚሆን ወልደ እግዚአብሔርን ስለመውደድህ ሕዋሳቶችህ በደም ቢታለሉ ለዓለም በሚያበራ የምስጋናው ውበት እንጸባረቁ፡፡ ድንቆችህን ስንቱን አወራለሁ ተጋድሎህንስ ስንቱን እናገራለሁ ለመናገር ድንቅ ነውና፡፡

፴ ደስ ያለህ ሕጻን ቂርቆስ ሆይ የተሸከመችህ ማኅፀን የከበረች ናት ያጠቡህ ጡቶችም የከበሩ ናቸው ቡሩክ ፍሬ የሆነ ብፁዕ ቂርቆስ ያፈራባት ዕለት ምንኛ የከበረች ናት፡፡
የንጉሥ አድራሻ የመንፈስቅዱስ ማደሪያ ቂርቆስ የተመሠረተባት ዕለት ምንኛ የከበረች ናት አሁንም ይህን ቡሩክ ሕጻን የወለደችልን ኢየሉጣን እናከብራታለን፡፡
፴፩ ንዕድ ክብርት ኢየሉጣ ሆይ ለመንፈስቅዱስ ንጹህ ማደሪያ ለበረከትም መዝገብ ሆንሽ ክብርት ኢየሉጣ ሆይ ለጸሎት ሠረገላ ለምስጋና ማረፊያ ነሽ ንዕድ ሆይ ለመጻሕፍት ቃል መዝገብ ለሃይማኖት ሽቱ ሙዳይ ነሽ፡፡ ክብርሽን አደንቃለሁ የተሰጠሽንም ጸጋና ክብር እናገራለሁ፡፡

በቅድስና በንጽሕና ያጌጥሽ ነሽ በሁሉም ዘንድ ፍጽምት ሆንሽ ክብርሽን መፈጸም የሚቻለው እንደበት እንደምን ያለ ነው የልጅሽንም የገድሉን ዜና መስማት የሚቻለው ጆሮ እንደምን ያለ ነው:: መስንቆ ለጆሮ፣ የሙሽራ ጌጥ ለዓይን፣ መልካም ጣዕም ለአፍ፣ ሽቱም ለአፍንጫ የወይን ፈሳሽ ለጉረሮ ያማረ እንደሆነ እንዲሁ ከጣዕሙ የተነሣ አጥንትን የማያለመልም የሕጻን ቂርቆስን ገድል መሰማትም ፈጽሞ ያማረ ነው:: የቅዱሳንና የሰማዕታትን ዜና መስማት የሰሚዎችን ልብ ደስ ያሰኛልና፣ ይልቁንም ንዑድና ክቡር የሚሆን የሕጻን ቂርቆስን ዜና መስማት ያሰደስተልና:: እግዚአብሔር የጸሎታቸውን በረከት ይስጠን ንዕድ ክብርት የአምላክ እናት በሆነች በእመቤታችን ልመና በቅዱሳንና በሰማዕታት በማያነቀላፉ ትጉሀን መላእክትና ሊቃነመላእክትም ልመና በቅዱስ ቂርቆስና በእናቱ በቅድስት ኢየሉጣም ልመና የጥምቀት ልጆች የሆንን ሁላችንን ይጠብቀን ለዘላለሙ አሜን::

//

# ክፍል ፪

## መጽሐፈ ገድል

### ምዕራፍ ፩

፩ በአብና በወልድ በመንፈስቅዱስም ስም አንድ አምላክ በሚሆን የማር ቂርቆስን ገድል የእናቱ የኢየሉጣንና የሌሎችንም በእስክንድሮስ መኰንን ዘመን ሰማዕትነትን የተቀበሉ የአሥራ አንድ ሺህ አራት መቶ ሠላሳ አራት ሰማዕታት ዜና መጻፍን እነሆ እናስከተላለን፤ በዚያ መኰንን ዘመን በኪልቅያ አብያተክርስቲያናት ላይ ታላቅ ስደት ሆኗልና፡፡

፪ በዚያም ዘመን ኢየሉጣ የምትባል አንዲት ሴት ነበረች፤ ይህችም ሴት ከልጅነቷ ጀምራ እግዚአብሔርን የምትፈራ ነበረች ስደትን በሰማች ጊዜ መኰንኑን ስለመፍራት ከሮም ሀገር ሸሽታ የኪልቅያ ክፍል ወደሆነች ወደጠርሴስ ደረሰች ከዚያም ተቀመጠች፡፡

፫ ስለዚህም ስደት ከማቴዎስ ወንጌል ስለጌታችን ልደትና ስደት ያለውን ነገር እናመጣ ዘንድ የኅሊናችን መንፈስ ግድ አለን፡፡

፬ ጌታ ኢየሱስ ክርስቶስም በይሁዳ ቤተልሔም በንጉሥ ሄሮድስ ዘመን በተወለደ ጊዜ እነሆ ሰብአ ሰገል የተወለደው የአይሁድ ንጉሥ ወዴት ነው? ኮከቡን በምሥራቅ አይተን ልንሰግድለት መጥተናልና እያሉ ከምሥራቅ ወደ ኢየሩሳሌም መጡ፤ ንጉሥ ሄሮድስም ሰምቶ ደነገጠ፤ ኢየሩሳሌምም ሁሉ ከእርሱ ጋር፡፡

፭ የካህናትንም አለቆች የሕዝቡንም ጻፎች ሁሉ ሰብስቦ ክርስቶስ ወዴት እንደሚወለድ ጠየቃቸው፡፡

፮ እነርሱም አንቺ፡ በተልሔም የይሁዳ ምድር ከይሁዳ ገገርዎች ከቶ አታንሺም ሕዝቤን እስራኤልን የሚጠብቅ ንጉሥ ከአንቺ፡ ይወጣልና ተብሎ በነቢይ እንዲህ ተጽፎአልና በይሁዳ ቤተልሔም ነው አሉት፡፡

፯ ከዚህ በኋላ ሄሮድስ ሰብአሰገልን በሥውር ጠርቶ ኮከቡ የታየበትን ዘመን ከእነርሱ በጥንቃቄ ተረዳ ወደ ቤተልሔምም እነርሱን ሰድዶ ሂዱ ስለ ሕጻኑ በጥንቃቄ መርምሩ ባገኛችሁትም ጊዜ እኔ ደግሞ መጥቼ እንድሰግድለት ወደእኔ ተመልሳችሁ ንገሩኝ አላቸው፡፡

፰ እነርሱም ከንጉሡ ዘንድ ይህን ሰምተው ሄዱ እነሆም በምሥራቅ ያዩት ኮከብ ሕጻኑ ባለበት ላይ መጥቶ እስኪቆም ድረስ ይመራቸው ነበር። ኮከቡንም ባዩ ጊዜ በታላቅ ደስታ እጅግ ደስ አላቸው። ወደቤትም ገብተው ሕጻኑን ከእናቱ ከማርያም ጋር አዩት፤ ወድቀውም ሰገዱለት ሣጥኖቻቸውንም ከፍተው እጅ መንሻ ወርቅና ዕጣን ከርቤም አቀረቡለት ወደ ሄሮድስም እንዳይመለሱ በሕልም ተረድተው በሌላ መንገድ ወደ ሀገራቸው ሄዱ።

፱ እነርሱም ከሄዱ በኋላ እነሆ የጌታ መልአክ በሕልም ለዮሴፍ ታይቶ ሄሮድስ ሕጻኑን ሊገድለው ይፈልገዋልና ተነሣ ሕጻኑንና እናቱን ይዘህ ወደ ግብጽ ሽሽ እስከነግርህም ድረስ በዚያ ተቀመጥ አለው እርሱም ተነስቶ ሕጻኑንና እናቱን በሌሊት ያዘና ከጌታ ዘንድ በነቢይ ልጄን ከግብጽ ጠራሁት የተባለው እንዲፈጸም ወደ ግብጽ ሄደ፤ ሄሮድስም እስኪሞት ድረስ በዚያ ኖረ። ማቴ ፪ : ፩ - ፲፭

፲ ይህንንም አምላካዊ የወንጌል ቃል ያለምሳሌ አንተወውም። ምሳሌውም እንዲህ ነው። ቀናተኛ ሄሮድስና በደለኛ እስክንድሮስ እነሆ በበደል ተባበሩ፤ ድንግል ማርያምና ክብርት ኢየሉጣም በስደት ተካከሉ፤ ማር ሕጻን ቂርቆስም ለበጎ ሥራው ሁሉ መሠረትና መጀመሪያ ለሆነው ለጌታ ለኢየሱስ አምሳያ ሆነ። ጌታ ሕጻን ሆኖ እንደተሰደደ ሕጻን ሳለ ተሰድዷልና ስደትን ከመቀበሉ ጀምሮ ከገሃነማዊ ሞት ሕይወት የሆነውን ስለጽድቅ መሞት እስከመቀበል ድረስ ጌታውን ያልመሰለበት ግብር የለም። የጠርሴስ ሀገርም ግብጽን መሰለቻት። ቀድሞ ይህን ለሚያህል ሀብት የተዘጋጀች ያልነበረች ግብጽ አነኳት። የማርያም ልጅ ስለእኛ የሚሸሽ ሆኖ በርሷ ዘንድ ተቀምጧልና ግብጽ የምታበራውን ያህል ፀሐይ አያበራም። ስለኛ የሸሸውን ሕጻን ግብጽ ተቀበለችው ያን ጊዜም ዘመን የማይቆጠርለት ዓለምንም ሁሉ የፈጠረ ሲሆን ሥጋና ደምን ከእኛ ነሥቶ ስለእኛ ሕጻን በሆነ በዚያ ሕጻን ክብር ከበረች።

፲፩ ፈርቶ እንደሸሸ ግን አናስብም የሕጻኑ ስደት ዲያብሎስን እንዳሳደደው አናስባለን እንጂ። ዲያብሎስን ለሕጻን ቂርቆስ እንደ ጨዋታ አደረገው። ባለምሳሌ ሰሎሞን ኃጢአተኛ ሰው የሚያሳድደው ሳይኖር ይሸሻል ምሳ ፳፰፡፩ እንዳለ ድምፁን በመስማት የተነሣ የሚሸሽ ሆኗልና።

፲፪ ወደ ብርቱ ሰው ቤት መግባት ገንዘቡንም መበርበር የሚቻለው ማንም የለም፤ ገንዘቡ ሁሉ የሚድንበትን ነፍጡን ይዞ ቅጥሩን ይጠብቃልና፤ የሚበረታታበት በመጣ ጊዜ ግን ያቸንፈዋል የሚተማመንበት ነፍጡን ይገፍፈዋል። ምርኮውንም ይወስድበታል (ሉቃ ፲፩፡ ፳፩፡ ፳፪) እነሆ ስሙ ከፍ ያለ ኢየሱስም ለማሳት የበረታ ሰይጣንን አቸነፈው።

ደካማም አደረገው ጥበቡንም አፈረሰ ማቸነፍ ነፍጡንም ለሕጻን ቂርቆስ ሰጠበት፣ ምርኮውንም ወሰደ ይኸውም አገዛዙን ማጥፋትና የኀጢአትን እሾህ መስበር የመታጀሩና አዳም የሰማው የመገዳደሩ ቃል መድከም ነው፡፡
፲፫ እነሆ ይህን ኃይል በማር ቂርቆስ ላይ በአክሊል ገለጠ ሄሮድስ ለገደላቸው ሕጻናት አሊቃቸው ሕጻን ቂርቆስ ነው፣ እኒህ ሁሉ በመሞት ይተካከሉታል የሥላሴን ስም በማስተማር ግን አይተካከሉትምና፡፡ ሞታቸውም በፈቃዳቸው አይደለም ሄሮድስ ክርስቶስን ሊገድለው ይፈልገው ነበርና ከእነርሱ አንዱ ቢሆን ብሎ ክርስቶስን ሲፈልግ ገደላቸው እንጂ፡፡ ቂርቆስ ግን በአደባባይ ቆሞ የሥላሴን ስም አስተማረ ሥላሴን ስለማያምለክም በፈቃዱ ሞተ፡፡

፲፬ እጅ መንሻ ያመጡ ሰብአሰገልንም አሊቃቸው ቂርቆስን ለሰላምታ እጅ የነሡት ሥላሴን ስለማያምለክም ከእርሱ ጋር በመሞት አንድ የሆኑ አስራአንድ ሺህ አራት መቶ ሠላሳ አራቱ ሰማዕታት መሰሉአቸው፡፡

## ምዕራፍ ፪

፩ የሸሸችው መኰንን እስክንድሮስ እነሆ ወደዚያች ሀገር ደረሰ ወታደሮቹም ክርስቲየኑን ፈለጉአቸው፡፡ ያን ጊዜም ወታደሮቹ ክብርት ኢየሉጣን ያዙአት ወደ መኰንን እስክንድሮስም ዘንድ አደረሱአት እነኋት ይህች ሴት መድኃኒተኛ ናት በሀገር ሁሉ መድኃኒት ታደርጋለች አይጠቅሙም ነፍስም የላቸውም ብላ ለአማልክቶችህ እንዳይሠው ሰዎችን ትከለክላለች አሉት፡፡
፪ እስክንድሮስም ይህን ሰምቶ አንቺ ከማን ወገን ነሽ ዘመድሽስ ማን ነው ሀገርሽስ ወዴት ነው ንገሪኝ አላት፡፡

፫ ክብርት ኢየሉጣም መለሰች አለችውም የእኔስ ወገኔ የኢቆንዮን ሀገር ሰዎች አለቃ ኢሳዊሮስ ነው፡፡ የዘር ሐረጌም ከጥንት የመንግሥት ነው፡፡ እንጌ ቤናዊት የምሆን እኔም ከቤተመንግሥት ወገን ነኝ አንተን ስለፈራሁ እስከዚህች ሀገር ድረስ ሸሸሁ ዛሬ ግን እነሆ በእጅህ ውስጥ ነኝ፡፡

፬ መኰንኑም በእጄ እንዳለሽ ካወቅሽስ ለአማልክቶቼ ሠዊ አላት ክብርት ኢየሉጣ ግን እኔ ለረከሱ አማልክት አልሰግድም አለችው፡፡ እሱም ከሁሉ በፊት እስኪ ስምሽን ንገሪኝ አላት፣ ክርስቲያናዊት ነኝ አለችው፡፡

፭ መኰንኑም ከእኔ ጋር እንዲህ ያለ መመላለስ አይጠቅምሽም ነገር ግን እንዳትሞቺ ስምሽን ንገሪኝ አላት። ክብርት ኢየሉጣም ክርስቲያናዊት ነኝ አላልሁምን በሰው ዘንድ የምጠራበትን ስሜን ከፈለግህ ግን እነሆ ስሜ ኢየሉጣ ነው አለችው።

፮ መኰንኑም ለአማልክቶቼ ሠዊ አላት እርሷ ግን ከዚህ በፊት ለረከሱ አማልክት የሠዋሁበት ጊዜ የለም ከእንግዲህም አልሠዋም አለች። መኰንኑም ትሠዊ ዘንድ ያለቀና የተቆረጠ ነገር ነገርሁሽ ለአማልክቶቼ ካልሠዋሽ ግን የተለያዩ አሰፈሪ መከራዎችን አመጣብሻለሁ አላት።

፯ ክብርት ኢየሉጣም አለች፣ ይህን ልታደርግ ከወደድህ ሦስት ወራት የቆሩትን የሦስት ዓመት ልጅ (ሕጻን) ፈልገው ወደአንተ ያመጡት ዘንድ ሰዎችን ወደሀገር ላክ እርሱም እኔና እርሱ የምናመልከውን አምላክ ይነግርሀልና፣ ሕጻኑም መጥቶ አማልክቶችህን እናምልካቸው ቢለኝ እንኳ አንተና ዘመዶችህ አምልኩአቸው እንጂ እሺ በጀ አልልህም፣ እኔ ለአምላኬ ለእግዚአብሔር እገዛለሁ።

፰ መኰንኑም የሦስት ዓመት ልጅ /ሕጻን/ እንዲፈልጉ ወታደሮቹን ወደ ከተማ ላከ የሀገሩ ሰዎች ልጆቻቸውን ሠውረዋልና አላገኙም ከዚያም ከከተማ ቅጽር በውጭ በፀሐይ መውጫ ወዳለ ዱር /ጫካ/ መጡ። የክብርት እየሉጣን ልጅ ቅዱስ ቂርቆስን አገኙት ወታደሮችም ይህ ሕጻን ስንት ዓመት ይሆነዋል ብለው የሀገሩን ሰዎች ጠየቁአቸው ከሦስት ዓመት ሦስት ወራት የጐደሉት ሕጻን ነው ይህም ሕጻን ከኢቆንዮን ሀገር ወደዚህ የሸሸች የአንጌቤን ሴት የሆነች የዚያች ክርስቲያናዊት ልጅ ነው አሉአቸው።

፱ ወታደሮቹም ሕጻኑን ያዙት ይህ ሕጻን ከክርስቲያን ወገን ነውና ለመኰንኑ የሚነግረው ነገር አያጣም ብለው ወደ መኰንኑ ወሰዱት።

፲ ወደ መኰንኑም ባደረሱት ጊዜ መልኩ የሚወደድ ደምግባቱ ያማረ እንደሆነ አይቶ በግልጥ ወደደው ደስ ያለህ ሕጻን ሆይ ሰላም ላንተ ይሁን አለው። ሕጻኑም መልሶ እውነት ብለሀል እኔ በአምላኬ ደስታ ደስተኛ ነኝ አንተ ግን ደስታ የለህም እግዚአብሔር ኃጢአተኞች ደስታ የላቸውም ብሏልና አለው።

፲፩ መኰንኑም አንተ ሕጻን ስትሆን አንዲት ነገር ሳልጠይቅህ እንደምን ይህን ያህል ነገር ትመልስልኛለህ አለው። ማር ቂርቆስም አለው ከዚህ

የሚበዛ ነገር እነግርሀለሁ:: ስሙ ይመስገንና አምላክ ክርስቶስ ስለእኔና እንደኔ ስላሉት እንዲህ ብሏልና ከሁሉ በፊት ይይዙአችኋል በሸንጎዎችም ወደነገሥታትና ገዢዎች ይወስዱአችኋል ያሥሩአችኋል ስሜ በእናንተ ይሆን ዘንድ ይህ ሁሉ ስለስሜ ያገኛችኋል የምትናገሩትንም በልባችሁ እንዳታስቡ ዕወቁ ሊከራከሩአችሁ በማይችሉ ገንዘብ እኔ አንደበትንና ጥበብን እሰጣችኋለሁ፣ ዘመዶቻችሁና ወንድሞቻችሁ ስለስሜ ይነሡባችኋል ይገድሉማችኋል ነገር ግን ከራሳችሁ ጠጉር አንዲቷ እንኳ አትጠፋም በመታገሣችሁም ነፍሳችሁን ትቤዧታላችሁ:: ማቴ ፲ :፲፯ :፳፪

፲፪ መኰንኑ እስክንድሮስም ሕጻኑን ስምህ ማን ነው አለው የከበረ ቂርቆስም ከጠራ ምንጭ ከማይጠፋም የውኃ ጉድጓድ የፈሰሰሁ ውኃ የክርስቲያን ወገን ነኝ አለ:: መኰንኑም እንዳትሞት ስምህን ንገረኝ አለው:: ሕጻኑም አለው እኔ የክርስቲያን ወገን ነኝ እናቴ የሰየመችኝን ካህኑም ባጠመቀኝ ጊዜ የሰየመኝን ስሜን ከፈለግኸው ግን ቂርቆስ ነው::

፲፫ መኰንኑም ቂርቆስን እሺ ብለህ ለአማልክቶቼ ሠዋ ጐልማሳ በሆንህ ጊዜ በአማልክት በት አለቃ አድርጌ እሾምሀለሁ ከገዢዎችም ነገሥታት ይልቅ በብዙ ትከብራለህ ከነርሱም ብዙ ወርቅና ብር ትቀበላለህ አለው::

፲፬ ሕጻን ቂርቆስ ግን የሰይጣን መልእክተኛ ሆይ ከእኔ ራቅ ወርቅና ብርህ ለጥፋት ይሁንህ ከእኔ ጋር የእግዚአብሐር ገንዘብ የሆነ የሕጻን እእምሮ እያለ በገንዘብ ብዛት የምታቸንፈኝ ይመስልሀልን እነሆ ልብህ በእግዚአብሔር ፊት የቀና አይደለምና በብርሃናዊ ዓለም እድል ፈንታ የለህም አሁንም ከክፋትህ ተመለስ የልብህንም ክፋት ቢያርቅልህ ወደ እግዚአብሔር ለምን በመራራ መርዝና በዐመፃ እሥራት ውስጥ ሆነህ አይሀለሁና::

፲፭ መኰንኑም አንተ ሕጻን ያስተማረህ ማንነው አባትህ ነውን ወይስ እናትህ ወይም ይህን ነገር ያስተማረህ ሌላ ነውን አለው የከበረ ሕጻንም ታላቅና ዝንጉ ሽማግሌ እንደምን ይህን ትጠይቀኛለህ፣ አባትና እናቴ አላስተማሩኝም ሌሎችም አልነገሩኝም ሥላሴ አስተማሩኝ እንጂ አሁንም ለሦስት ዓመት ሦስት ወራት የቀሩኝ ሕጻን ሳስተምርህ አንተ ልትሰማው የማትችለውን የሥላሴን ነገር እነግራለሁ አለው:: የማር ቂርቆስ ዓመታቱ እኒሁ ናቸው በወር ቁጥርም ሠላሳ ሦስት ወራት ናቸው:: ሠላሳውም ወራት ሥላሴን ያስተምራሉ::

፲፮ ዳግመኛም ሠላሳ ወራት ለስሙ ምስጋና ይሁንና በአምላክ ዘመነ ሥጋዌ ይመሰላሉ፣ ወንጌላዊው ሉቃስ የጌታ ኢየሱስ ዕድሜው ሠላሳ ዓመት ያህል ሆኖት ነበር እንዳለ /ሉቃ ፫ ፡፳፫/ ሦስት ወራትም ለስሙ ስግደት ይሁንና ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ወንጌልን በዓለም ላስተማረባቸው ሦስት ዓመታት ምሳሌዎች ሆኑ::

፲፯ ከዚህ በኊላ መኰንኑ ሕጻኑን በእናታችሁ ተሸክማችሁ ወደ ምድር ጣሉት በየተራም አምሳ አምሳ ጅራፍ ግረፋት ብሎ ወታደሮቹን አዘዘ::

፲፰ ጽኑ ግርፋትን ሲገርፋት ዓይኖቹን ወደ ሰማይ አቅንቶ አቤቱ አመሰግንሀለሁ በውሳጤያዊና በአፍአዊ አካሌ /በልቤም በአንደበቴም/ አመሰግንሀለሁ ለአንተ ምስጋና ይገባልና የማትሞት ሕያው ንጉሥ ሆይ በዚህ ዓለም ጥልቅ ወደ ሆነ ችግርና የፍርድ ቦታ እንዳልወርድ ወዳንተ እጸልየለሁ ብሎ በታላቅ ድምጽ ወደ እግዚአብሔር ጸለየ::

፲፱ ታጋሹም ሕጻን ይህንን ሲጸልይ የሚገርፉት አላቋረጡም እርሱም ከምድር እንደወደቀ ነበር:: ነገር ግን አንዲትም የግርፋት ምልክት በሥጋው ላይ አልተገኘም::

፳ እነሆም ስሙ ሕያው የሆነ ጀርባዬን ለግርፋት ጉንጬንም ለጥፊ ሰጠሁ ፊቴንም ከምራቅ አፍረት አልመለስሁም / / ያለ አምላኩን መሰለ::

፳፩ አባቶቹም ሐዋርያት ስሙ ይቅርባይ ስለሆነ ስለ ክርስቶስ ግርፋትን ተቀበሉ፣ መገረፋቸውንም የሥራቸው ዜና (መጽሐፍ) እንዲህ ብሎ ነገረን:: ሊቀካህናቱና የሰዱቃውያን ወገን ከእርሱም ጋር የነበሩት ሁሉ ተነሡ ቅንዓትም መላባቸው:: በሐዋርያትም ላይ እጃቸውን ጭነው በሕዝቡ ወኅኒ ውስጥ አኖሩአቸው የጌታ መልአክ ግን በሌሊት የወኅኒውን ደጅ ከፍቶ አወጣቸውና ሂዱና ቆማችሁ የዚህን ሕይወት ቃል ሁሉ ለሕዝብ በመቅደስ ንገሩ አላቸው በሰሙም ጊዜ ማልደው ወደ ምኲራብ ገብተው አስተማሩ::

፳፪ ሊቀ ካህናቱና ከእርሱ ጋር የነበሩት ግን ሸንጎውንና የእስራኤልን ልጆች ሽማግሌዎች ሁሉ በአንድነት ሰበሰቡ ሐዋርያትንም ያመጡአቸው ዘንድ ወደ ወኅኒ ላኩ ሌሎምችም መጥተው በወኅኒው አላገኙአቸውም ተመልሰውም ወኅኒው ፈጽሞ በጥንቃቄ ተዘግቶ ጠባቂዎችም ደጃፎቹን ሲጠብቁ አገኘን በከፈትን ጊዜ ግን በውስጡ አንድ ስንኳ አላገኘንም አሉአቸው::

፳፫ የምኲራብ አዛዦችና የካህናት አለቆችም ይህን ነገር በሰሙ ጊዜ እንጃ ይህ ምን ይሆን? እያሉ ስለ እነርሱ አመነቱ::

፳፭ አንድ ሰውም መጥቶ እነሆ በወኅኒ ያኖራችኋቸው ሰዎች በምኩራብ ቆመው ሕዝቡን እያስተማሩ ናቸው ብሎ ነገራቸው።

፳፮ ከዚህ በኋላ የምኩራብ አዛዥ ከሎሌዎች ጋር ሄዶ አመጣቸው በኃይል ግን አይደለም፡ ሕዝቡ እንዳይወግሩአቸው ይፈሩ ነበርና አምጥተውም በሸንጎ አቆሙአቸው። ሊቀካህናቱም በኢየሱስ ስም ለማንም እንዳታስተምሩ አልከለከልናችሁምን? እነሆም ኢየሩሳሌምን በትምህርታችሁ ሞላችኋት የዚያን ሰው ደም በእኛ ታመጡብን ዘንድ ትፈልጋላችሁን አላቸው።

፳፱ ጴጥሮስም ከሐዋርያት ጋር መለሰላቸው አላቸውም ከሰው ይልቅ ለእግዚአብሔር ልንታዘዝ ይገባል እናንተ በእንጨት ላይ ሰቅላችሁ የገደላችሁትን ኢየሱስን የአባቶቻችን አምላክ አስነሣው እርሱን እግዚአብሔር ለእስራኤል ንስሓን የኃጢአትንም ሥርየት ይሰጥ ዘንድ ራስም መድኃኒትም አድርጎ በቀኙ ከፍ ከፍ አደረገው እኛም ለዚህ ነገር ምስክሮች ነን ደግሞም እግዚአብሔር ለሚታዘዙት የሰጠው መንፈስቅዱስ ምስክር ነው።

፴፫ እነርሱም ሲሰሙ በጣም ተቆጡ ሊገድሉአቸውም አሰቡ። ነገር ግን በሕዝብ ሁሉ ዘንድ የከበረ የሕግ መምህር ገማልያል የሚሉት አንድ ፈሪሳዊ በሸንጎ ተነሥቶ ሐዋርያትን ጥቂት ፈቀቅ እንዲያደርጉአቸው አዘዘ፣ እንዲህም አላቸው፣

፴፭ የእስራኤል ሰዎች ሆይ ስለእነዚህ ሰዎች ምን እንደምታደርጉ ለራሳችሁ ተጠንቀቁ፡ ከዚህ ዘመን አስቀድሞ ቴዎዳስ እኔ ታላቅ ነኝ ብሎ ተነሥቶ ነበርና አራት መቶ የሚያህሉ ሰዎችም ከእርሱ ጋር ተባበሩ፣ እርሱም ጠፋ የሰሙትም ሁሉ ተበተኑ እንደምናምንም ሆኑ ከዚህ በኋላ ሰዎች በተቆጠሩበት ዘመን የገሊላው ይሁዳ ተነሣ ብዙ ሰዎችንም አሸፍቶ አስከተለ እርሱም ጠፋ የሰሙትም ሁሉ ተበታተኑ፡ አሁንም እላችኋለሁ ከእነዚህ ሰዎች ተለዩ ተውአቸውም ይህ ምክር ወይም ይህ ሥራ ከሰው እንደሆነ ይጠፋልና ከእግዚአብሔር እንደሆነ ግን ታስተውአቸው ዘንድ አትችሉም ከእግዚአብሔር ጋር እንዲሚጣሉም አትሁኑ፡ እሺ አሰኛቸው።

፵ ሐዋርያትንም ጠሩአቸው ገረፉአቸውም በኢየሱስም ስም እንዳይናገሩ አዘዘው ፈቱአቸው።

፴ እነርሱም ስለ ስሙ ያጉሳቍሉአቸው ዘንድ መንፈስቅዱስ አድሏቸዋልና
ከሸንጎው ፊት ደስ እያላቸው ወጡ፣ ዕለት ዕለትም በመቅደስና በቤታቸው
ስለኢየሱስ እርሱ ክርስቶስ እንደሆነ ማስተማርንና መስበክን አይተዉም
ነበር። ሐዋ ፭ ፡፵፩ ፡፵፪
የቅዱስ ቂርቆስ ጸሎቱና በረከቱ ለዘላለሙ ከእኛ ጋር ይሁን አሜን።

## ምዕራፍ ፫

፩ መኰንኑም የተወደደ ሕጻን ትዕግሥቱን አደነቀ ከነገሩ መጣፈጥና
ከአንደበቱ መቀላጠፍ የተነሣም ዕፁብ ዕፁብ አለ መናገር እንደማይችል
ሕጻን ሳይሆን ሥልጣን እንዳለው ሰው ያስተምረዋል ይገሥጸዋልና። እናቱ
ኢየሉጣንም ወደሸንጎ ያመጡአት ዘንድ ወታደሮችን አዘዘ አመጡአትም
ሕጻኑን ግን አራቁት።

፪ መኰንኑም ኢየሉጣን እነሆ ሕጻኑ ልጅሽ በአማልክቶቼ አመነ አላት
እሷም ከቃሉ እስማ ዘንድ ወዲህ አምጣው አለች፣ ሕጻኑንም አመጣው።

፫ ኢየሉጣም ልጇን በመኰንኑ ፊት ቆሞ ባየችው ጊዜ እጆቿን ወደ
ሰማይ ዘርግታ እግዚአብሔርን እንዲህ ስትል አመሰገነችው አቤቱ ዓለምን
ሁሉ የያዝህ የይቅርታ ባለቤት ሰማይን የዘረጋህ ምድርንም የፈጠርህ
ባሕርና ነፋስን የወሰንህ ሰማይን በከዋክብት ያስጌጥህ ምድርን በአበባና
በፍሬዋ የሸለምህ በጊዜው ሁሉ ስምህን አመሰግናለሁ ከማኅፀኔ የወጣ ሕጻን
ልጄን የምስጋናህን ነገር እንዲናገር አድርገኸዋልና ነቢዩ ዳዊት ከልጆችና
ከሚጠቡት አፍ ምስጋናን አዘጋጀህ ዳግመኛም የቃልህ ነገር ያበራል
ሕጻናትንም ጥበብ ያናግራል እንዳለ መዝ ፰፡፪፣ ፻፲፰፡፻፴

፬ የዚህንም ቃል ስሙ ይመስገንና ጌታችን አባት ሆይ የሰማይና
የምድር ጌታ ይህን ከጥበበኞችና ከአስተዋዮች ሠውረህ ለሕጻናት
ስለገለጥህላቸው አመሰግንህለሁ አዎን አባት ሆይ ፈቃድህ እንዲሁ ሆኗልና
ብሎ ማቴ አተመው ፲፩፡፳፭

፲፭ ያንጊዜም ልጁ ሆይ ይህ ልጅሽ እንደሚበልጥሽ የማይጠፋውንም አክሊል ከተቀበሉ ብዙዎች ሰማዕታት እንደሚበልጥ እመኚ ነገር ግን በፊታችሁ ካለው ከዚህ መከራ የተነሣ አንድ ጊዜ ወደኋላ ታፈገፍጊያለሽ ይህ ልጅሽ ግን ይቀድምሻል ወደእኔ በመጸለዩ ማሸማጠጥን ከአንቺ ላይ አስወግዷልና የሚል ቃል ከላይ ወደ እሷ መጣ።

፲፮ በዚህ ጊዜ ክብርት ኢየሉጣ ልጁ ሆይ እግዚአብሔርን እንጂ ማንን ትፈራለህ ከአምላክስ በቀር ማንን ታምናለህ አለችው። የታመነ ሕጻንም እኔም ከንቺ ጋር እሆናለሁና አትፍሪ ስሙ ከፍ ከፍ ይበልና ከእኔ አሮጌውን ሰው አውጥቶ የማያረጀውንና የማይጠፋውን አዲሱን በጥምቀቱ ያልበሰኝ ኢየሱስን አምነዋለሁ አላት።

፲፯ መኰንኑም አንተም እናትህም መሞትን መረጣችሁን አለው መከራን ለመቀበል የጨከነ ሕጻንም ይህ ምክርህ ለፍርድ ወደገሃነም ይወስደናል ሃይማኖታችን ግን ስሙ ወደከበረ ሕይወታችን ወደ ኢየሱስ ክርስቶስ ታደርሰናለች አለው። መኰንኑም ብረት ሠሪዎቹን ሰናፍጭና ጨው አምጥታችሁ በአፍንጮቻቸው ጨምሩ አላቸው እንዲሁም አደረጉ።
፲፰ ያንጊዜም በአምላኩ የሚመካ ቂርቆስ ቃልህ ለጉሮሮዬ ጣፋጭ ነው ከማርና ከሥኳር ይልቅ ለአፌ ጣፈጠኝ /መዝ ፻፲፰፡፻፫/ ብሎ አስምቶ ተናገረ ነቢዩ ሕዝቅኤል እንዳለ በሠላሳኛው ዓመት በአራተኛው ወር ከወሩም በአምስተኛው ቀን በኮቦር ወንዝ በምርኮኞች መካከል ሳለሁ ሰማያት ተከፈቱ የእግዚአብሔርንም ራእይ አየሁ ንጉሡ ዮአኪን በተማረከ በአምስተኛው ዓመት በወሩም በአምስተኛው ቀን የእግዚአብሔርን ቃል በከላዳውያን ሀገር በኮቦር ወንዝ ወደ ቡዝ ልጅ ወደ ካህኑ ወደ ሕዝቅኤል መጣ አየሁም፤ መጽሐፍ የያዘ እጅ ወደእኔ ተዘረጋ በፊቴም ገለጠ በውስጥና በውጭም ተጽፎበት ነበር። መጽሐፋም ልቅሶና ኀዘን ዋይታም ይል ነበር የሰው ልጅ ሆይ አፍህ ይብላ በምሰጥህም በዚህ መጽሐፍ ሆድህም ይሙላ አለኝ እኔም በላሁት በአፌም ውስጥ እንደማር ጣፈጠ
ሕዝ፩ ፡፩ ፲፡፪፤፱-፲፤፲፫፡፪-፲
፲፱ መኰንኑም ለአማልክቶቼ ሠው ካልሠዋችሁ ግን እገድላችኋለው አላቸው። ሕጻን ቂርቆስ ግን መከራህ የአብ የምስጋናው ጸዳል የሚሆን የክርስቶስን ስም ማምለክን የሚያስተወን ይመስልሀልን እነሆ እርሱ ከእኛ ጋር አለና ይረዳንማልና ስለዚህ ነገር ቁጣህን አንፈራም አለው።

፳ ይህች አምላካዊት ጥበብ ምንኛ ድንቅ ናት! ከመንፈስቅዱስ ጸጋ እንጂ የቂርቆስ የልሆነች ይህችስ አሳብ ምንኛ ደስ የምታሰኝ ናት! ይህን የተናገር ከኅሊናው አንቅቶ አይደለም እንዲህም ያለ ጥበብና ዕውቀት ለሕጻን የሚቻል አይደለምና። ይህን ጥበብ ከወዴት አገኘ? ከእናቱ ጡት ነውን?

ወይስ ከወዳጆቹ ከሕጻናት ጋር ከመጫወት ነውን? ከሜዳ አበባ ነውን ወይስ ከትንሽ (ከደቃቅ) አሸዋ? የሕጻን ልማዱ ነውና፡ አሳዳጊዎቹ የሜዳ አበባ በሰጡት ጊዜ ግምጃ ልብስ የሰጡት ይመስለዋል ትንሽ አሸዋም ቢሰጡት ትልቅ ወርቅ የሰጡት ይመስለዋል።

፲፩ የዚህ ምልክት የሜዳ አበባ አሸዋም እንዲህ (ያለ ነገር አይናገርም። የሕጻንስ ልማዱ የልብ መዘንጋት ነው ከሕጻናት ጋር መጫወቱም ጥቅም የለውም። እንደርሱ ያለው እንዲህ ያለውን ጥበብ እንደምን ይናገራል ይህ ግን ከአምላካዊ ኃይል የተነሣ ተደረገ የመንፈስቅዱስም ጸጋ በሕጻን ቁርቆስ ላይ እነሆ ኀይልን ገለጠች ብርቱ ጉልማሳም አደረገችው። ከሽማግሌዎች ይልቅ መርጣዋለችና።

፲፪ ሕጻኑም ዳግመኛ አለው መልካም የመከርከኝ መሰለህን ስለአንተና እንዳንተ ስላሉት ጣፋጩን መራራ መራራውን ጣፋጭ ነው ለሚሉ ወዮላቸው ብሏልና። መኰንኑም ክፉ ቁጣ ተቆጣ፣ ውጪው በሽበት ያጌጠ በውስጡ ግን የሕጻናት ልብ ያለው ሽማግሌ እነሆ በጠጉር መንጣት የከበረ ሆነ፣ እርሱ ግን በስንፍናው ገፋት እነሆም ውበቷን ስላቃለለ ክብሯንም ስለጣለ ለቁርቆስም መሳቂያና መሣለቂያ ስለሆነ ሽበቱ ትፋረደዋለች።

፲፫ ከዚህም በኋላ ወታደሮቹን አሥራአራት የተሳሉና እንደ እሳት ፍም የጋሉ ረጃጅም ብረቶችን /ችንካሮችን/ አምጥታችሁ ሰባቱን በእናቱ ላይ ሰባቱን ደግሞ በሕጻኑ በሁለንተናው ጨምሩ፣ ይሞት ዘንድ ሁለቱን በዓይኖቹ፣ ሁለቱን በአፉ አንዱን በልቡ ሁለቱንም በሌላ በኩል አድርጉ አላቸው። እኒያም ብረቶች በቅዱሳኑ ሥጋ ውስጥ ተቸነከሩ በእግዚአብሔር ትእዛዝ ግን የችንካሮቹ ግለት ጠፋ እንደ ክርምት በረዶም በረደ ቀዘቀዘም።

፲፬ መኰንኑም ወታደሮቹን ወደ ወህኒ ወስዳችሁ እሠሩአቸው የማደርገውንም እስክመክር ድረስ በሩን ዝጉባቸው አላቸው በሚከብዱ ሰንሰለቶች አሠሩአቸው። ያንጊዜም አቸናፊው ሕጻን በአምላኩ በእግዚአብሐር ፊት ዘመረ አለም፣ አቤቱ ልመናዬን ቸል ቸል አትበል የኃጢአተኞችና የአመፀኞች አፍ በኔ ላይ ይከፈታል በሽንገላም አንደበት ስለእኔ ይናገራልና አንተም አቤቱ ስለስምህ የመልካሙን ነገር ምልክት ከእኔ ጋር አድርግ የሚከሰሱኝ እፍረትን ይልበሱ እፍረትንና ጉስቁልናንም እንደግምጃ ልብስ ይጐናጸፉ ከእኔም ጋር የመልካሙን ነገር ምልክት አድርግ የሚጠሉኝም አይተው ይፈሩ አቤቱ አንተ አምላኬ ደስ አሰኘተኸኛ ልና።

፲፭ የከበረም ሕጻን ይህን እያለ ወደ ወህኒ ቤት ገቡ ምሽትም ነበረ:: ልመናዬን በፊትህ እንደ ዕጣን ተቀበለኝ ብሎ የምሽት መዝሙር ይዘምር ጀመር ዳግመኛም ልዑልን መጠጊያህ አደረግህ፣ ክፉ ነገር ወደ አንተ አይቀርብም መቅሠፍትም ወደ ቤትህ አይገባም አለ /መዝ፻:፬-፲/ ከዚህም በኋላ መጸለይን ፈጽመው አንቀላፉ እኩለ ለሊትም በሆነ ጊዜ የከበረ ሕጻን ተነሣና ከንፈሮቼን እገልጣለሁ አንደበቴም ምስጋናህን ይናገራል ብሎም አመሰገነ ::

፲፮ ዳግመኛም አቤቱ ስምህን አመሰግነ ዘንድ በእኩለ ለሊት እነሣለሁ አለ:: /መዝ፻፲፰:፷፪/

፲፯ ከዚህም በኋላ ማመስገኑና መለመኑን ፈጸሙ:: ሰይጣን የብርሀን መልአክ መስሎ መጣ የሚያቸንፈው ሕጻን ቂርቆስንም የአምላክህ የእግዚአብሔር ምስጋናውን ስለምን አበዛህ? እነሆ እግዚአብሔር ልመናህን ቸል አለ ገዢው ንጉሥ ቢያዝዝህ እሺ በለው አትጠራጠርም ወዳጁ ትሆናለህ በሰማያትም ክብርን ታገኛለህ ብዬ ቃልን እንድነግርህ ላከኝ አለው::

፲፰ አዋቂ የሆነ ሕጻንም የመተንኰል አመጣጡን አውቆ ምክርህ የከፋ ከቅዱሳንም ጋር ዕድል ፈንታ የሌለህ ዲያብሎስ ከእኔ ወግድ ለስሙ መገዛት ይሁንና ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ አሥሮ አንተ ወደ ገለጥከው የገሃነም ጥልቅ ያውርድህ አለ::

፲፱ ያን ጊዜም አፍሮ ሸሸ፣ የሰይጣንም ልማዱ እንዲህ ነው የብርሃን መልአክ የሚመስልበት ጊዜ አለ፣ /፪ቆሮ፲፩:፲፬/ በባለራእዮችም አንደበት የሐሰት መንፈስ የሚያሳድርበት ሰውንም የሚያስትበት ጊዜ አለ:: ስለዚህም ነገር በሦስተኛው የእስራኤል ነገሥታት የታሪክ መጽሐፍ የተጻፈ የቆየ ታሪክ እናመጣለን፣ የይሁዳ ንጉሥ እዮሳፍጥ በሦስተኛው ዓመት ወደ እስራኤል ንጉሥ ወደ አክዓብ እንደወረደ::

፳ ንጉሥም ባለሟሎቹን ሬማት ዘገለዓድ የእኛ እንደሆነች አታውቁምን እስከመቼስ ከሶርያ ንጉሥ እጅ ሳንወስዳት ዝም እንላለን፣ አላቸው ኢዮሣፍጥንም በሬማት ዘገለዓድ እንዋጋ ዘንድ ከእኔ ጋር ትወጣለህን አለው:: ኢዮሣፍጥም አምን ከአንተ ጋር እሄዳለሁ እኔ እንዳንተ ነኝ ወታደሮቼ እንደወታደሮችህ ፈረሶቼም እንደፈረሶችህ እንዲሁ ናቸው:: አለው:: ዳግመኛም ኢዮሣፍጥ የእስራኤልን ንጉሥ በዚህች ቀን እስኪ ወደ እግዚአብሐር እንጠይቅ የሚመልስልንንም እንይ አለው::

፳፩ አክዓብም ነቢያትን አራት መቶ የሚያህሉ ሰዎችን ሰብስቦ ወደ ሬማት ዘገለዓድ ለሰልፍ ልወጣን ወይስ ልቅር? አላቸው:: እነርሱም:- እግዚአብሐር ጠላቶችህን በእጅህ አሳልፎ ይሰጥሀልና ውጣ አሉት:: ኢዮሣፍጥ ግን እግዚአብሔርን የሚጠይቅ ሌላ የእግዚአብሔር ነቢይ በዚህ የለምን አለ::

የእስራኤልም ንጉሥ ኢዮሣፍጥን ወደ እግዚአብሔር ሊጠይቅልን የሚገባ ሰወ በዚህ አለ፣ ነገር ግን ስለእኔ ክፉ እንጂ መልካም ትንቢት አይናገርምና እጠላዋለሁ ስሙም የይምላዕ ልጅ ሚክያስ ነው አለው። የይሁዳም ንጉሥ ኢዮሣፍጥ ንጉሥ እንዲህ አይበል አለ። የእስራኤልም ንጉሥ ከጃንደረቦቹ አንዱን ጠርቶ ሂድ ፈጥነህም የይምላዕን ልጅ ሚክያስን አምጣው አለው።

፳፪ የይሁዳ ንጉሥ ኢዮሣፍጥ የእስራኤል ንጉሥ አክዓብ ሁሉም እንያንዳንዳቸው ቀይ ግምጃ ልብስ ለብሰው በሰማርያ በር መግቢያ አጠገብ በአደባባይ በዙፋኖቻቸው ላይ ተቀምጠው ነበር። የሐሰት ነቢያትም በፊታቸው ትንቢት ይናገሩ ነበር የክንዓን ልጅ ሴዴቅያስም ሁለት የብረት ቀንዶች ሠርቶ እግዚአብሔር እንዲህ ይላል ሶርያውያንን እስኪጠፉ ድረስ ትወጋቸዋለህ። ነቢያትም ሁሉ ንጉሥ ሆይ ወደ ሬማት ዘገለዓድ ውጣ ታቸንፋቸውማለህ እግዚአብሔርም የሶርያን ንጉሥ በእጅህ አሳልፎ ይሰጥሀል እያሉ ትንቢት ይናገሩ ነበር።

፳፫ ወደ ሚኪያስም የተላከው መልእክተኛ እነሆ ነቢያት ሁሉ በአንድ አፍ ሆነው ስለንጉሥ መልካም ይናገራሉ አንተም ቃልህ እንደ ቃላቸው ይሁን መልካምም ተናገር አለው። ሚኪያስም ሕያው እግዚአብሔርን እግዚአብሔር ያለውን ካልሆነ በቀር እንደማልናገር በእርሱ እምላለሁ አለ። ሚኪያስም ወደ ንጉሡ ደረሰ። ንጉሥመ ሚክያስን፡- መልካም ነገሮች ቢደረጉልኝ ወደሬማት ዘገለዓድ ለሰልፍ ልውጣን ወይስ ልቅር አለው እርሱም ንጉሥ ሆይ ውጣ ታቸንፋለህም እግዚአብሔርም ጠላቶችህን በእጅህ ይሰጥሀል አለው።

፳፬ ንጉሡም፡- እግዚአብሔር ከገለጠልህ በቀር የሐሳብህን እንዳትነግረኝ በእግዚአብሔር አምልሀለሁ። አለው። ሚክያስም አለው እስራኤልን ጠባቂ እንደሌላቸው በጎች በተራሮች ላይ ተበትነው አየሁአቸው እግዚአብሔርም ለእነዚህ ጌታ የላቸውም ሁሉም እያንዳንዱ በሰላም ወደ ቤቱ ይመለስ አለ። የእስራኤልም ንጉሥ የይሁዳ ንጉሥ ኢዮሣፍጥን ይህ ሰው ክፉ እንጂ መልካም እንደማይናገርልኝ አላልሁህምን አለው።

፳፭ ሚኪያስም አለ እንግዲህስ የጆሮህን በር ከፍተህ የእግዚአብሔርን ቃል ስማ የእስራኤል አምላክ እግዚአብሔርን በዙፋኑ ተቀምጦ የሰማይም ሠራዊት በዙሪያው በቀኙና በግራው ቆመው አየሁት። እግዚአብሔርም ወደ ሬማት ዘገለዓድ እንዲወጣ በዚያም በፊቱ እንዲወድቅ አክዓብን

የሚያስተው ማን ነው? አለ ከዚህ በኋላ የሐሰት መንፈስ መጣ በእግዚአብሐርም ፊት ቆሞ እኔ አስተዋለሁ አለ። እግዚአብሔርም በምን ታስተዋለህ? አለው እርሱም በነቢያት አፍ የሐሰት መንፈስ እሆናለሁ አለ። እግዚአብሐርም አምን ይቻልሀል እንዲሁም አድርግ አለው እነሆ እግዚአብሐር ባንተ ዘንድ ባሉ በነቢያትህ ሁሉ አፍ የሐሰትን መንፈስ አድርጎአል እግዚአብሔርም ስለአንተ ክፉ ተናግሮብሀል።

፳፮ ከነናዊው የክንዓንም ልጅ ሴዴቅያስ ቀርቦ በአንደበትህ እንዳህ የተናገርህ የእግዚአብሔር መንፈስ ከእኔ መቼ ራቀ? ብሎ ጉንጮቹን ጸፋው። ሚክያስም መልሶ እነሆ በዚያ ቀን ልትሸሸግ ወደ እልፍኝህ በገባህ ጊዜ ታያለህ አለው። የእስራኤልም ንጉሥ ብላቴኖቹን ሚክያስን ወስዳችሁ ለከተማይቱ ሹም ለአሞን ለንጉሥም ልጅ ለዮአስ ሰጡአቸው በሰላምም እስክመለስ ድረስ የመከራ እንጀራ እንዲበላ የመከራም መጠጥ እንዲጠጣ በወህኒ እሠሩት ብሏችኋል በሉአቸው አላቸው። ሚክያስም በደኅና ብትመለስ እግዚአብሐር በእኔ አድሮ የተናገረህ አይደለም አለው።

፳፯ የእስራኤልም ንጉሥና የይሁዳ ንጉሥ ወደ ሬማት ዘገለዓድ ወጡ። የእስራኤልም ንጉሥ የይሁዳ ንጉሥ ኢዮሣፍጥን እነሆ እኔ ልብሴን ለውጬ ወደ ሰልፍ እገባለሁ አንተ ግን ልብስህን ልበስ አለው። የእስራኤልም ንጉሥ ልብሱን ለውጦ ወደሰልፍ ገባ። የሶርያም ንጉሥ ሠላሳ ሁለቱን የሠራዊት የጭፍራ አበጋዞች አለቆች ከእስራኤል ንጉሥ ብቻ በቀር ታናሽም ቢሆን ወይም ታላቅ ከማናቸውም ጋር አትግጠሙ ብሎ አዝዞ ነበር።

፳፰ የጭፍራ አበጋዞችም የይሁዳ ንጉሥ ኢዮሣፍጥን ባዩት ጊዜ ይህ የእስራኤልን ንጉሥ ይመስላል ብለው ሊዋጉት ከበቡት። የይሁዳ ንጉሥ ኢዮሣፍጥም ጮኸ እግዚአብሔርም አዳነው የጭፍራ አበጋዞችም የእስራኤል ንጉሥ እንዳልሆነ ባዩ ጊዜ ከእርሱ ተመለሱ። የእስራኤል ንጉሥ አክዓብን ግን ከሬማት ወገን የሆነ አንድ ሰው አይቶ አወቀው። በቀስትም ወጋው። የእስራኤልም ንጉሥ በመገጣጠሚያው መሀል ተወጋ ከብረቱም ጽናት የተነሣ ቀስቱ አልፎ ወደ ሆዱ ገባ የእስራኤልም ንጉሥ የሠረገለኞቹን አለቃ እጅህን መልስ ከሰልፍም መካከል አውጣኝ አለው። በዚያን ቀን በዚያም ሰዓት ጦሩ ተበተነ።

፳፱ የእስራኤልም ንጉሥ በሶርያ ንጉሥ ፊት ከጧት እስከ ምሽት ድረስ በሠረገላው ላይ ተደግፎ ነበር፣ ደሙም በሠረገላው ውስጥ ፈሰሰ፣ ፀሐይም በገባች ጊዜ ንጉሥ ሞተ አዋጅ ነጋሪም ንጉሥ ሞቷልና ሁሉ እያንዳንዱ ወደሀገሩ ወደርስቱ ይሂድ ብሎ በሰልፍ መካከል አስምቶ ተናገረ፩ ነገ ፳፪:፱-፴፮

፴፲ ለጽድቅ ወደሚጋደል ወደቂርቆስ በመጣ ጊዜ ግን ተሸነፈ አፈረም ዳግመኛም ተመልሶ በዚህ ብታቸንፈኝም ምንም ቃል እንዳይናገርህ የምትወድደውንም አክሊል እንዳትቀበል የመኰንኑን አንደበት እሥራለሁ በዚህም ብታቸንፈኝ ወደ እናትህ ልብ ገብቼ ከቀናይቱ ጉዳና ፈቀቅ አደርጋተለሁአለው። ማር ቂርቆስ ግን ሰይጣን ከእኔ ወግድ ጌተዬ ኢየሱስ ክርስቶስ የሳፍርህ አለው።

፴፲፩ ያን ጊዜም ሰይጣን አፈረ፤ እንደጢስም በንኖ ከወህኒ ወጣ። ሰይጣን ከእኔ ወግድ በማለቱም መምህሩ ክርስቶስን መሰለው።

፴፲፪ ይህም በወንጌል የተጻፈ ነው ከዚህ በኋላ ከዲያብሎስ ይፈተን ዘንድ መንፈስ ጌታ ኢየሱስን ወደ ምድረ በዳ ወሰደው። አርባ ቀንና አርባ ሌሊትም ጦሞ ተራበ ፈታኙም ቀርበ

፴፲፫ የእግዚአብሐር ልጅ ከሆንክ እኒህ ደንጊያዎች እንጀራ እንዲሆኑ በል አለው ጌታ እየሱስም መልሶ ሰው ከእግዚአብሔር አፍ በሚወጣ ቃል ሁሉ እንጂ በእንጀራ ብቻ እንደማይኖር ተጽፏል አለው።

፴፲፬ ከዚህ በኋላ ዲያብሎስ ወደ ቅድስት ከተማ ወሰደውና በመቅደስ ጫፍ ላየ አቁሞ መላእክቱን ስለአንተ ያዝልህል እግርህንም በድንጋይ ከቶ እንዳትሰናከል በእጃቸው ያነሡሀል ተብሎ ተጽፏልና የእግዚአብሐር ልጅስ ከሆንክ ወደታች ራስህን ወርውር አለው። ጌታ ኢየሱስም መልሶ ዳግመኛ እግዚአብሔር አምላክህን አትፈታተነው ተብሎ ተጽፏል አለው።

፴፲፭ ዳግመኛም ዲያብሎስ እጅግ ረጅም ወደሆነ ተራራ ወሰደው የዓለምንም መንግሥታት ሁሉ ክብራቸውንም አሳይቶ ወድቀህ ብትሰግድልኝ ይህን ሁሉ እሰጥሀለሁ አለው። ያን ጊዜ ጌታችን ኢየሱስ ሰይጣን ከእኔ ወግድ ለአምላክህ ለእግዚአብሔር ስገድ እርሱንም ብቻ አምልክ ተብሎ ተጽፏልና አለው ከዚህ በኋላ ዲያብሎስ ተወው እነሆም መላእክት ሊያገለግሉት መጡ ማቴ ፬፥፩-፲፩

## ምዕራፍ ፬

፩ ሕጻኑም እናቱን ራሳችንን ለገንዘብ አንስጥ ነጣቂም መዝገባችንን እንዳይሠርቅ ተግተን እንጸልይ አላት:: በወህኒም ውስጥም ያሉት ምክሩን በሰሙ ጊዜ ይህን ያህል ጥበብ ለሕጻኑ የሰጠውን እግዚአብሔርን አመሰገኑት::

፪ ከዚህም በኋላ ሕጻኑ እንዲህ ብሎ አመሰገነ አቤቱ ማረኝ፣ ነፍሴ አንተን ታምናለችና፣ ጉዳት እስኪታልፍ ድረስ በክንፎችህ ጥላ እታመናለሁ:: ወደሚረዳኝ አግዚአብሔር፣ ወደ ልዑል እግዚአብሔር እጮኻለሁ ከሰማይ ልኮ አዳነኝ

፫ ለረገጡኝም ውርደትን ሰጣቸው እግዘብሔር ቸርነቱንና እውነቱን ላከ:: ነፍሴን ከአንበሶች መካከል አዳናት:: ደንግጬ ተኛሁ፣ የሰው ልጆች ጥርሳቸው ጦርና ፍላጻ፣አንደበታቸውም የተሳለ ሾተል ነው:: አምላክ ሆይ በሰማያት ላይ ከፍ ከፍ በል፣ ክብርህም በምድር ሁሉ ላይ ትሁን:: መዝ ፶፯:፩-፭

፬ በነጋም ጊዜ አቤቱ እንደ ቸርነትህ መጣን ማረኝ እንደ ምሕረትህም ብዛት መተላለፌን ደምስስ ..... ያን ጊዜ በመሠዊያህ ላይ ፍሪዳዎችን ይሠዋሉ አለ:: መዝ ፶:፩:፲፱

፭ ምስጋናውንም ከፈጸመ በኋላ መኰንኑ ከወህኒ አውጥቶ ከሸንጎ አቆማቸው:: ሕጻኑንም ለአማልክቶቹ ሠዋ አልልህም፣ ነገር ግን ከሥቃይ እንድትድን በቃልህ ለሰራጺስ አጥናለሁ በል አለው:: መከራን ለመቀበል የጨከነ ሕጻን ግን የሰይጣን መልእክተኛ አንተ እንደ ልማድህ ሠዋ፣ እርሱ ወደ ልብህ ሳይገባ አስቀድሞ አምላክህ አምላከ እንዳልሆነ አምላኬ ነግሮኛ ልና ይፍረስ እንጂ ዕጣን ይታጠንለት አልልም አለው::

፮ በዚያን ጊዜም መልአክ መጥቶ መሠዊያውን አፈረሰ አሥራአራቱንም የጣዖት ምስሎች ጣላቸው ቀጠቀጣቸውም እንደትቢያም ሆኑ:: ሕጻኑም የአሕዛብ አማልክት የሰው እጅ ሥራዎች ናቸው:: አፍ አላቸው አይናገሩምም ዓይን አላቸው አያዩምም፣ ጆሮ አላቸው አይሰሙምም፣ አፍንጫ አላቸው አያሸቱምም፣ እጅ አላቸው አይዳስሱምም፣ እግር አላቸው አይሄዱምም፣ በጉሮሮአቸውም አይናገሩም በአፉቸውም ውስጥ እስትንፋስ የለም፣ የሚሠሩአቸውም /የሚያምኑባቸውም/ ሁሉ እንደ እነርሱ ይሁኑ:: መዝ ፻፲፫:፲፪-፲፮

፯ ጥበበኛው ሕጻንም:- አማልክትህን ከጠደቁበት አንሥተህ ቅባትና ጨው በተነከሩ የጥጥ ጨርቆች ጠቅልላቸው:: ሬሳቸውንም መርዳት ቢችሉ እስከ ሳባት ቀን ድረስ ጠብቃቸው አለው::

መኰንኑም ሕጻኑ እንዳዘዘው አደረገ በውስጣቸው ግን ድምጽ አልተገኘም እንደ ትቢያ ናቸውና፡፡

፳ ከዚህ በኋላ መኰንኑ ብረት ሠሪ አመጣ የማሠቃያ መሣሪያውንም እንዴት እንደሚሠራ ሊያዝዘው ወደደ፡፡ ሰይጣን ግን አስቀድሞ መኰንኑን ዲዳ አደርገዋለሁ ብሎ እንደተናገረ በመኰንኑ ልብ ውስጥ ገብቶ አንደበቱን ዘጋው ሕጻኑ አክሊል ስለሚቀበልበት ሥቃይም መናገር ተሳነው፡፡

፱ ማር ቂርቆስም አንጥረኛውን እኔና እናቴ በመኰንኑ ዘንድ መከራ የምንቀበልበትን አሰጨናቂ ማሠቃያ ልትሠራ ትችላለህን ይህ መኰንን ግን የሚያውቀው የለም አለው፡፡ አንጠረኛውም ሕጻኑን፡- የማደርገውን አንተ ንገረኝ አለው፡፡

፲ ሕጻኑም አለው፡፡ ሰፋታቸው ክንድ የሚያህሉ ሁለት ምላጮችን አንዱን ለእኔ አንዱን ለእናቴ ሥራ፡፡ ራስ መቆልመሚያና መስበሪያ፣ አንገት መምቺያና ማሠሪያ ሥራ፣ ዓይን ማውጫና አፍንጫ መጭነኛ መገጣጠሚያ ማውጫና መፍቻ ምላስ መቁረጫ ጥርስም መንቀያ ጐን መፉቂያ፣ ጉልበትና ጭን መስበሪያ፣ ጅማቶችን የሚቆርጥና የሚበጥስ የሚበትንም ሥራ፣ ለእኔም በላም አምሳያ የብረት መቀመጫ ሥራልኝ በውስጡም ሦስት ቀዳዳዎችን ሦስትም ችንካሮችን አድርግ ከሚጠሩት ሰዎች ፈጽሞ የማይለይ ሥሉስ የሚልም ጽሑፍ በውስጡ ጻፍ፡፡

፲፩ ዳግመኛም ሁለት ጠምዝዞ የሚያሰጨንቅ መሣሪያ ሥራ ሁለት መጋዝ ብረት ምጣድም አዘጋጅ አንድ ተላቅ ጋንም ሥራ በዚያም ጋን ውስጥ አንገት የሚቆለምምና የሚያንቅ መንኩራኩር ሥራ ሆድ ዕቃ የሚበረብር የብረት እጀታም አድርግበት እኔ መከራ የምቀበልባቸው እኒህ ናቸው፣ ሌሎች ያሰብኳቸው ሥቃዮች ካሉም አንተው ሥራቸው፡፡ ያን ጊዜም ብረት ሠሪው ደነገጠ መኰንኑንም እንዲህ ያለ ጥበብ ከሽማግሌዎችም አልሰማሁም፣ ነገር ግን እኒህን የማሠቃያ መሣሪያዎች የሚሠሩ አንድ መቶ ጥበበኞችን አምጣ እኔ ብቻዬን ግን አልችልም መሥራቱንም አላውቅም አለው መቶ ጥበበኞችንም አመጣ በመሥራት አገዙት በአርባ ቀንም ፈጸሙ፡፡

፲፪ መከራ ለመቀበል የጨከነ ሕጻንም እስከ አርባውቀን ድረስ መጸለይን አላቋረጠም፡፡ በወህኒ ያሉትንም ሃይማኖትን ባስተማራቸው ጊዜ ከዚህ ችግር ሊያድናቸው በሚችል በሕያው እግዚአብሔር አመኑ፡፡ ከርሱም ጋር በወህኒ የነበሩት አራት መቶ ሠላሳ ናቸው፤፤ የሕጻኑንም ታናሽነትና የትዕግሥቱንም ብዛት አይተው አደነቁ፡፡ በእግዚአብሔር የማመናቸውንም ኃይል ጨመሩ፡ ድንቅን የምታደርግ አቤቱ አንተ በእውነት የተመሰገንህ ነህ ዘወትርም ለባለሚሎችህ ረዳት ትሆናለህ እኛም ሁላችን በአንተ አመንን፣ አቤቱ ዓለምን የያዝህ አምላካችን ከእጅህ በረከትን እንድንቀበል አድለን መተላለፋችንን ላንተ እንታመናለን አንተ ግን አታስብብን በእውነት አምላክ የሆንህ እግዚአብሔር ሆይ በአንተ አምነናል እያሉ ተቀመጡ፡፡

፲፫ ንዑድ ክቡር ቂርቆስም ይህን በሰማ ጊዜ በተሰጠው ጸጋ ጸና፣ ከእርሱም ጋር የነበሩት:: ከአርባ ቀንም በኋላ እንዲህ ሆነ የማሠቃያ መሣሪያውን ወደሸንጎ አመጡት መኰንኑም ሐጻኑን በእኔ ዘንድ የምታደርገው ይህ ነገር ጨዋታ አይምሰልህ እነሆ የማሠቃያ መሣሪያው ሁሉ ተሠርቶ በፊትህ ተዘጋጅቷል አለው::

፲፬ የከበረ ሕጻንም መልሶ:- አፍረት የሌለህ ክፉ በደለኛ ሆይ እኔ አዝጌ ባሠራሁት የማሠቃያ መሣሪያ ታስፈራራኛለህን? አለው:: መኰንኑም እየተዘባበተ በምትሐትህ ነውን ይህን ይሠሩ ዘንድ ሙያተኞቼን ያዘዝኳቸው? በኢየሱስ ክርስቶስ ስም የምታቸንፈኝ ይመስልሀልን? አለው እውነት ብለሀል ይህ የማሠቃያ መሣሪያ ምንድር ነው አንተ የዘነጋህ ብራሄል ነህና እነሆ ዘወትር የሚረዳኝ ኢየሱስ ክርስቶስ አለኝና ቁጣህ አላስደነገጠኝም አለው::

፲፭ መኰንኑም ወስዳችሁ የእሳት ፍም በራሳቸው ላይ ጨምሩባቸው ብሎ አዘዘ ይህንንም ባደረጉ ጊዜ የእሳቱ ፍም ጠፋ እንደሚያንጸባርቅ አክሊልም ሆነላቸው:: ያን ጊዜም የወህኒ ቤቱን እንዲከፍቱ አዘዘ:: እኒያም አራት መቶ ሠላሳው ሰዎች መጡ በአንድነትም በሸንጎው እየሮጡ በታላቅ ድምፅ መኰንኑን እኛ ሁላችን የክርስቶስ አገልጋዮች ክርስቲያን ነን አሉት:: መኰንኑም የምታምኑት ምን አይታችሁ ነው? አላቸው፣ ቅዱሳኑም ልብ የሌለህ ሰነፍ! ስሙ ይመስገንና ክርስቶስ ያዘጋጀልንን አክሊላት አታይምን? ስለእኒህም አክሊላት ሃያ አምስት ልመናዎችን እንለምናለን አሉት::

፲፮ ከዚህ በኋላ መኰንኑ:- ከከተማ ውጪ አውጥተው ቸብቸቧቸውን እንዲቆርጡ አዘዘ:: በቆርጡአቸውም ጊዜ ፊታቸውን በመስቀል ምልክት አማተቡ:: በጥር ወር በአሥራአራተኛው ቀን በሰይፍ ተከለሉ:: በሕጻኑም ላይ መኰንኑ ተቆጥቶ ረጅም ወንበር አምጥተው ችንካሮችን ከትከሻው እስከ ተረከዙ ችንክረው እንዲተክሉት አዘዘ:: ቸነከሩትም ሌላም ችንካር በግራ ትከሻው ሦስቱንም ችንካሮች ከራሱ እስከእጆቹ ችንክረው በወንበሩ ታችኛ አካል እንዲጸፉት አዘዘ::

፲፯ መኰንኑም ሕጻኑን:- በእውነት አምላክ ካለህ ከእጄ ያድንህ አለው:: ያን ጊዜም መልአክ ከሰማይ መጥቶ ችንካሮቹን ከሕጻኑ ነቅሎ በመኰንኑ አካል ጨመረው:: መኰንኑም ደንግጦ አንተ ሐጻን አምላክ እንዳለህ ዛሬ አወቅሁ በአምላክህም ቸርነት ዛሬ ፈውሰኝ አለው:: የከበረ ሕጻንም አንተ እንደማታምን አውቃለሁ ነገር ግን ስለሚያምኑት ሰዎች

፲፰ በአምላኬ ስም ዛሬ እፈውስሀለሁ አለ:: ከዚህም በኋላ ሕጻኑ እጁን ዘርግቶ ቸንካሮቹን ነቀለለት ፈወሰውም:: ያን ጊዜም መኰንኑ ዓለም የሚስማማባችሁ አልፋና ሰራኤል አጵሎንና አቴና አርአያም የተመሰገናችሁ ናችሁ እኔም በእናንተ ተፈወስሁ ብሎ ጮኸ::

፲፱ የከበረ ሕጻንም ዛሬስ አቸነፍከኸኝን ዳግመኛም ወደ እኔ ትመጣለህ? አለው መኰንኑም የማሠቃያ መሣሪያውን ሁሉ አውጥታችሁ በሥጋቸው ላይ ጨምሩት እነሆ አምላካቸው ይዘባበትብኛልና:: ከዚህ ሥቃይ ግን ሊያድናቸው አይችልም አለ:: ወታደሮችም የማሠቃያ መሣሪያዎችን ሁሉ አምጥተው እንዲጨነቁ ከራሳቸው እስከ እግር ጥፍራቸው በሰውነታቸው ጨመሩ ነገር ግን የማሠቃያ መሣሪያዎቹ ሊያስጨንቋቸው አልቻሉም::

፳ መኰንኑም ከማለዳ እስከ ስድስት ሰዓት ድረስ የማሠቃያ መሣሪያው ሁሉ ሊያሠቃያቸው እንዳልቻለ ባየ ጊዜ ተነሥቶ አንገት መቆልመሚያውን ከአገልጋዩ ተቀበለ፣ ፈጽሞ ይገድለው ዘንድ በሕጻኑ ላይም ሊወረወረው ወደደ:: ወደ ላይ ይዞ ሲወርድ ከእጁ ወድቆ አፍንጫውን በእጅጉ እስኪያሳምመው ድረስ ፊቱን ክፉኛ መታው:: ያን ጊዜም የከበረ ሕጻን ሳቀ፣ የሚያሠቃዩኝ ጠላቶቼ እነርሱ ደክመው ወደቁ፡ ሰይፋቸው ወደ ልባቸው ይግባ ቀስታቸውም ይቀጥቀጥ ያለው መዝሙር በእውነት አልዋሸም አለ::

፳፩ የእግዚአብሔር ጸጋ ቂርቆስን እንዲህ መገበችው የመኰንኑም ቁጣ በራሱ ላይ መለሰች:: ከፈጣሪው ባለሟልነትን ስላገኘ የእግዚብሔር መላእክት በዙሪያው የሚከታተሙለትን ታጋይ ሕጻን መርዳቷን እንተውና የእግዚአብሔር መግቦት የሰው ልጆችን ሁሉ ትከድናቸዋለች ታቅፋቸውማለች እኮን፣ ምስጋና ይሁንለትና እርሱን ግን ከኃጢአት ከነጹትና ዘወትር ሥራዎቹን ከሚመሰክሩ በቀር አየዩትም ይልቁንም ስለእሱ ወደጽኑ መከራ በገቡ ጊዜ የእግዚአብሔር መግቦት ትገለጥላቸዋለች:: ያን ጊዜም ድንገት በሚመጣ ተመስጦ በልዩ ልዩ አምሳል እስኪያዩት ድረስ ይረዱታል::
፳፪ እግዚአብሔር ይህን ለሚያቸንፉ ተጋዳዮች ያደርጋልና:: በኢዮብና በኢያሱ ወልደ ነዌ በሦስቱ ሕጻናትና በጴጥሮስ የእግዚአብሔር መግቦት በሰው አምሳል ተገልጣ ባስጨከነቻቸውና ባጸናቻቸው ቅዱሳንም ሁሉ እንደሆነ:: በእኒህ ቅዱሳትና ቅዱሳን ላይም በመግቦት መንገድ ከልዑል እግዚአብሔር ዘንድ ተደረገ ብንል ለዚህች እይታ በብዙ የተዘጋጁ ሆኑ:: በሕዝቡ መካከል እጅግ ጥቂት የሆኑ የቅዱሳን ሰማዕት ጭከናቸው ምሳሌ ይሁንልን::

፳፫ በብዙ ሥፍራዎች እነሆ ስለ ክርስቶስ ተጋደሉ ኃይላቸው ሲደክም በጭከና ሥቃዩ ብዙ በሆነ በብረት መታሠር ላይ በቆየ በሥጋም ታገሡ ይህችውም በጠባይዕት ያለች ግብር ናት እንዲህ ላሉት ሰዎች አምላካዊት መግቦት ሁሉ እያንዳንዱ ያውቅ ዘንድ ስለርሱ በመንገድ ሁሉ በመከራና በችግርም ሁሉ ለታገሡ ለእኒህ ቅዱሳን መላእክት ተገለጡ ማቸነፋቸው የመጨከናቸውም ምስጋና የጠላቶቻቸውም ማፈር እንዲገለጥልን ቅዱሳን በእኒህ ራእዮች በውሳኔ ሁሉ ላይ በመጠን የሚበረታቱ ሆነዋል፡፡ የሚቃረኗቸውም የሚቆጩና ከትዕግሥታቸው የተነሣ እንደ አውሬ የሚሆኑ ሆነዋልና፡፡

፳፬ ዓለምን ስለናቁና ስለ መጻተኞች፣ ስለታረዙት በበረሀም ስለዞሩት ምን ልንል ይገባል መላእክት ማደሪያና ማረፊያ አደረጉአቸው፡፡ ዘወትርም ወደ እነርሱ ይገባሉ ስለጭከናቸው ጽናት ስለ አካሄዳቸውም ማማር፣ ለአንድ ጌታ ወታደሮች እንደመሆናቸው፣ ከእነርሱም መካከል ከወዳጆቻቸው ጋር የሚሰበሰቡ አሉ፣ እነሆ በሕይወት ዘመናቸው ሁሉ በረሀን ወደዱት ማደሪያቸውንም በተራሮችና በዋሻዎች በፍርኩታዎችም አደረጉ ስለ ልዑል እግዚአብሔር ፍቅር ሰማያዊት መንግሥትንም ወደዱ፡- ምድራውያንን እንደናቋቸው ለመላእክት ጓደኞች ሆኑ፡፡ መላእክትም ፈቃዳቸውን ከእነርሱ የማይሸሽጉ ሆኑ በቀጥተኛ መንገድ አይደለም በጊዜ ሁሉ በመበቀል ይገለጡላቸዋል እንጂ ሊያደርጉት የሚገባቸውንም ያስተምሯቸዋል፡፡

፳፭ ልዩ ልዩ ተግባራትን የሚገልጡላቸው ጊዜ አለ የሚያስደቷቸውም ጊዜ አለ አንድ ጊዜ በሚዞሩ ጊዜ በመንገድ ይመሯቸዋል አንድ ጊዜም እንዳይወድቁ ከመከራዎች ይድኗቸዋል አንድ ጊዜ በዋሻዎች መፍረስ በምድር መሰንጠቅ ሊወድቁም ከደረሱ ደንጊያዎች የተነሣ ድንገት ከሚደርስባቸው ችግር ውስጥ ያወጡአቸዋል፡፡

፳፮ አንድ ጊዜም ጠላት በግልጥ በተጣላቸው ጊዜ እስኪያዩአቸው ድረስ ይገለጡላቸዋል ሲረዷቸውም እነሆ ልንረዳችሁ ተላክን ይሏቸዋል ማቸነፍንና መጨከንን መረጋጋትን ይሰጧቸዋል፡፡ አንድ ጊዜም በገድል ካገኛቸው ደዌ ቅዱሳኑን ያድኗቸዋል፡፡ አንድ ጊዜም ምግብ አጥተው በደከሙ ጊዜ በእጅ ዳሰሰው ወይም በቃል ተናግረው ያጸኑአቸዋል ኃይልና ድንቅንም ይሰጡአቸዋል፡፡

፳፯ ኀብስት የሚያመጡላቸው ጊዜ አለ ንፍሮም የሚያመጡላቸው ጊዜ አለ ስለ ዕረፍታቸውም ለሌሎች ይነግሩአቸዋል፡፡

፳፫ ቅዱሳን እኛን መመገባቸውን ጸድቃንንም መገብኘታቸውን በመቁጠር ነገርን ለማስረዘም ምን ውድ አለብን? ዳግመኛም እነርሱ ስለ ታናናሾች በሚሆን በታላላቆቹ ወንድሞች መንከባከብ ጸድቃንን ስለእኛ እንደሚንከባከቡ እንናገራለን:: ይህን ግብር ያስታወስነው የጻፍነውም ምስጋና ይግባውና እግዚአብሔር በእውነት ለሚሰምኑት ቅርብ እንደሆነ ሰዎች ያውቁና ልባቸው እርሱን በማመን ይጸና ዘንድ ነው::

## ምዕራፍ ፩

፩ ከዚህም በኋላ መኰንኑ ይህን ሕጻን መድኃኒቶቹ እንደ ጠቀሙት በአምላኬ ማልሁ አለ:: ማር ቂርቆስ ግን በአንተ ላይ ያደረ ሰይጣን በአምላኬ ኃይል እንደሚቸነፍ በአገዛዝና በባሕርይ መንግሥት አንድ በሆኑ በአብና በወልድ በመንፈስቀዱስም ስም ማልሁ አለው::

፪ መኰንኑም ወታደሮቹን ጠምዝዞ የሚያስጨንቀውን መሣሪያ አምጥታችሁ በአካላቸው ውስጥ ጨምሩት ፈጽማችሁም አሳምሟቸው አላቸው:: ያን ጊዜም ማር ቂርቆስ ዓይኖቹን ወደ ሰማይ አቅንቶ የመላእክት ጌታ ሆይ መጀመሪያ መጋደልን፣ መፈጸሙ ይቻለኛል ብዬ በፈቃዴ አልጀመርሁም አንዲት ሰዓት እንኳ ቢሆን መከራውን በኃይሌ አልታገሥሁም ቸርነትህ ትዕግሥትን ሰጠችኝ እንጂ:: አሁንም አቤቱ ሰይጣንን እንዳቸንፈው በፊትህም ምሕረትን እንዳገኝ ኃይልን ስጠኝ አለ ክብር ይግባውና ጌታችንና መድኃኒታችን ኢየሱስ ክርስቶስም ና ዋጋህን ላሳይህ ከዚህም በኋላ መኰንኑን ታሳፍረው ዘንድ ትሄዳለህ አለው::

፫ ከዚህ በኋላ ወደ ወህኒ አስገብተው አንድ ጊዜ በመጋዝ መገዙአቸው በሁለተኛው መመገዝ ሥጋቸውን ቆራርጠው ማር ቂርቆስ መኰንኑን አማልክቶችህን በቅባትና በጨው ጠቅልላቸው እንዳለው ቅባትና ጨው በተነከረ የጥጥ ጨርቆች ጠቀለሉአቸው:: ከዚያም ሥጋቸውን እንደ ትቢያ በተኑት::

፬ መኰንኑም በመቶ አንጥረኞች ላይ የተሾመ አንጥረኛው ድሜጥሮስን ሕጻኑን በብዙ ድካም አቸነፍሁት አለው፣ ድሜጥሮስም አማልክቶችህን ስለወደድካቸው ይህን ሁሉ አደረግህ አለ:: ያን ጊዜም እንጊቤናዊው አውሴብስ ከአሥር ሺህ ሰዎች ጋር ግርፋት ነበረችው እስክንድሮስም የሚከራከራቸው የተከተሉት አምስት መቶ ሰዎች ነበሩ:: ከዚህ በኋላ ጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ መንግሥተ ሰማያትን አሳየቸው ማር ቂርቆስንም ያሳየውን መንግሥቱን እንደሚሰጠው ቃል ኪዳን ገባለት:: ከሞትም አነሣው::

፳፩ ከዚህ በኋላ ወደ ብረትምጣዱ ሄደ የቅዱሳኑን ሥጋ ዳሠሠ በላያቸውም የኃይል መንፈስን እፍ አለባቸው ወደ ሸንጎ ሄዳችሁ መኰንኑን አሳፍሩት አላቸው እንዳዘዛቸውም ሄዱ የቅዱሳኑንም አንድነት አገኙ የከበረች ኢየሉጣ ግን በዚያ ሥፍራ በነበሩት አስራ አንድ ሺህ አሪት ሰዎች መካከል ማለፍ አቃታት።

፳፪ ያን ጊዜም የከበረ ሕጻን ቂርቆስ እናቱን እናቴ ሆይ ወደ መሬት አውርጂኝ አላት ከመሬትም ቆመ ከዚህ በኋላ ተበተኑ ሕጻኑም እናቱን ይዟት ወደ መኰንኑ ገባ። ታውቀናለህን እኛ እነ ማን ነን አሉት፣ መኰንኑም ፈርቶ እኔ አላውቃችሁም አለ። ይህንንም ያለው ሌሎች እንዲያምኑ ነው።

፳፫ ያንጊዜም የተባረከ ሕጻን አለው የሰይጣን ልጅ ክፋትና ተንኰልም የሞላብህ ለሎች እንዳያምኑ አላውቃችሁም ትለናለህን እኛ አንተ ያሠቃየኸን ሥጋችንንም ቆርጠህ ከብረት ምጣድ የጨመርከን አይደለምን ለስሙ መገዛት ይሁንና መድኃኒታችን ክርስቶስ አነሣን አለው። በዚያን ጊዜም አሥራ አንድ ሺህ አራቱ ሰዎች በእውነት የዚህ ሕጻንና የእናቱ አምላክ ከሞት ያነሣቸው እግዚአብሔር አንድ ነው ብለው አሰምተው ተናገሩ።

፳፬ መኰንኑም ያደረገው ሁሉ ምትሐት ነውና አትታወኩ ያደርጉም እንደሆነ ምልክት እጠይቃቸዋለሁ ሊያደርጉት ከቻሉ የተደረገው ሁሉ እውነት ነው አላቸው፡ ተአምረኛው ሕጻንም ፈጽሞ የሚሰጥ እግዚአብሐርን ለምነው አለው።

፳፭ መኩንኑም በእውነት ከሙታን ከተነሣችሁስ ጫማዩ ወጥቶ ቀድሞ ሕያው ሳለ እነደነበረ ይሁን አለው። ድንቅ አድራጊው ሕጻንም አቤቱ ሰማይና ምድርን የፈጠርህ አንተ ነህ ሰውንም በጥበብህ ፈጠርህ የሕይወትንም እስትንፋስ ሰጠኸው፣ አሁንም አቤቱ ደም ለሚጠጣ ለዚህ መኰንን የልመናውን ስጠው አንተ እግዚአብሔር የማትታይ ብቻህን አምላክ እንደ ሆንህ ያውቁ ዘንድ የሥራህንም ጥበብ እንዲያውቁ፣ መሠረት ሳያስቀድም ቤቱን የሚሠራ ማን ነው አንተ ግን እንዲህ አይደለም ሰማይን መፍጠርን አላስቀደምህም ምድርን በደቃቅ አሸዋ መሥራትንም አላስከተልህም አለ።

፳፮ ከዚህ በኋላ የመኰንኑ ጫማ ከእግሩ ወጥቶ ታላቅ በሬ ሆነ ከበሬውም አንገት ፍየል ወጣ ይህችም የማር ቂርቆስ ጸሎት ስለአልዓዛር በዮሐንስ ወንጌል አባት ሆይ ስለሰማኸኝ አመሰግንሀለሁ፡ ሁልጊዜም እንደምትሰማኝ አውቃለሁ፡ ነገር ግን አንተ እንዳልከኝ ያምኑ ዘንድ በዚህ ዙሪያ ስለ ቆሙት ሕዝብ ተናገርሁ አለ።

፳፯ ይህንንም ብሎ በታላቅ ድምጽ አልዓዛር ሆይ ወደ ውጭ ና በሎ ጮኸ የሞተውም እጆቹና እግሮቹ በመግነዝ እንደተገነዙ ወጣ ፊቱም በጨርቅ እንደተጠቀለለ ነበር ኢየሱስም

ፍቱትና ይሂድ ተውት አላቸው። ዮሐ ፲፩፡፵፩-፵፪ ያለውን የመምህሩን የክርስቶስን ጸሎት ትመስላለች።

፲፪ ተማሪው ቁርቆስም የመምህሩ የክርስቶስን መጽሐፍ እነሆ ተማረ ይኸውም በሬና ፍየል ማስነሣት ነው። አሥራ አንድ ሺህ አራቱ ሰዎችም ይህንን ባዩ ጊዜ አቤቱ አምላካችን አንተ ቻይና እውነተኛ ነህ ጉዳናህም ሁሉ የቀና ነው፡ ብለው ጮኹ። መኰንኑም ይህን ሁሉ በምትሐቱ ያደርጋልና አትታወኩ አላቸው። አንጌቤናዊ ቁርቆሰም በሬውና ፍየሉ ይበሉ ዘንድ ሣር ስጧቸው አሉ። በሰጧቸውም ጊዜ በሉ።

፲፫ መኰንኑም አርደው አሥራ አንድ ሺህ አራቱን ሰዎች ምሳ እንዲያበሏቸው አዘዘ ከጠገቡ ሌላም ምግብ ካልፈለጉ፣ የተደረገው ሁሉ እውነት ነው አላቸው። ከዚህ በኋላ ምሳው ተዘጋጅቶ አሥራአንድ ሺህ አራቱም ሰዎች ቀረቡ በልተውም ጠገቡ። ከፍየሉም ሥጋ ስድስት ቅርጫት ከበሬውም ሥጋ አራት ቅርጫት አስተረፉ። እግዚአብሔር ጥቂቱን ማብዛት ብዙውንም ማሳነስ እንደሚችል ሰዎች ያውቁ ዘንድ።

፲፬ መኰንኑም የተረፈውን ሥጋ ባየ ጊዜ ባለሟሎቹን ሌሎች አይተው እንዳያምኑ ይህን ሥጋ ከባሕር ጨምሩት አላቸው።

፲፭ ለስሙ ምስጋና ይሁንና የአንድ የክርስቶስን ሥራ የሠራ የማር ቂርቆስ ሥራውን እነሆ ልናደንቅ ይገባናል። የዚህንም ምልክት ቅዱስ ወንጌል እንዲህ ብሎ ያበስረናል። በመሸም ጊዜ ደቀመዛሙርቱ ወደ እርሱ ቀርበው ቦታው ምድረበዳ ነው። አሁንም ሰዓቱ አልፏል ወደ መንደሮች ሄደው ለራሳቸው ምግብ እንዲገዙ ሕዝቡን አሰናብት አሉት፡ ጌታ ኢየሱስም እናንተ የማበሉትን ስጧቸው እንጂ ሊሄዱ አይገባም አላቸው።
፲፮ እነርሱም ከአምስት እንጀራና ከሁለት ዓሣ በቀር በዚህ የለንም አሉት። እርሱም፡- እነዚያን ወደዚህ አምጡልኝ አላቸው። ሕዝቡም በሣር ላይ እንዲቀመጡ አዘዘ፣ አምስቱንም እንጀራና ሁለቱን ዓሣ ይዞ ወደ ሰማይ አሻቅቦ አየና ባረከ እንጀራውንም ቆርሶ ለደቀመዛሙርቱ ሰጣቸው፣ ደቀመዛሙርቱም ለሕዝቡ አቀረቡ። ሁሉም በልተው ጠገቡ፣ የተረፈውንም ቁርስራሽ አሥራ ሁለት መሶብ ሙሉ አነሱ። ከሴቶችና ከልጆችም ሌላ የበሉት አምስት ሺህ ወንዶች ያህሉ ነበር። ማቴ፲፬ ፲፭፡፳፩

፲፯ እነሆ ስሙ ሕያው የሆነ ክርስቶስ አምስት ሺህውን ሰዎች በአምስት እንጀራና በሁለት ዓሣ አጥግቦ አሥራ ሁለት መሶብ የመላ ቁርስራሽ እንዳተረፈ አራት ሺህውን ሰዎች በሰባት እንጀራ አጥግቦ ሰባት ቅርጫት

የመላ ቁርስራሽ እንዳተረፈ / / እንዲሁም ማር ቁርቆስም አሥራአንድ ሺህ አራቱን ስዎች አጥግቦ ከፍየሉ ሥጋ ስድስት ቅርጫት ከበሬውም ሥጋ አራት ቅርጫት አተረፈ።

፲፰ ከዚህ በኋላ መኰንኑ ባለመድኃኒት ጠርቶ መከራከሩን ነገሩንም መስማት አልቻልሁምና የዚህን ሕጻን ምላሱን ቁረጥ አለው። ቆረጠውም ተናጋሪ ሕጻን ግን መኰንኑን አንተስ ምላሴን የቆረጥህ ይመስልሀል እነሆ አንተና አባትህ ሰይጣን በስሕተታችሁ ውኃ ልታጠፉት የማትችሉትን የእሳታዊ አንደበት ከመንፈስቅዱስ ተቀበልሁ አለው። መኰንኑም በባለመድኃኒቱ ላይ ተቆጥቶ ለምን ምላሱን ከግንዱ አልቆረጥህም? ሥሩንስ በጥበብህ ሁሉ ለምን አልበጠስህም? አለው።

፲፱ ባለመድኃኒቱም መኰንኑን ጌታዬ ሆይ መላ ምላሱ እነሆ በእጄ አለ አንተም በዓይኖችህ እየው ሕጻኑ ግን ከተናገረ ምላስም ሳይኖረው ከፊተኛ ው ይልቅ አብዝቶ ከዘለፈህ እኔ ምን ላድርገው፤ ምላሱን ከሥሩ ቆርጬ መታሰቢያውን አጥፍቼ እንዳሳይህ ብትወድስ እርያ አምጣልኝ አለው። አመጣለት ምላሱን ቆረጠው እርያውም ፈጥኖ ሞተ። ስለዚህም መኰንኑ ባለመድኃኒቱን ከመቅጣት ተወው።

፳ የተጋ ቁርቆስ ግን በሃይማኖቱ ጸና የዳዊት ቤት ይፀናል እንደተባለ መኰንኑን መዝለፉን አጸና። እነሆም ማር ቁርቆስ የዳዊት ልጅ ስለሆነ የጸና ሆነ እስክንድሮስ ግን የሳኦል ቤት ይደክማል እንደተባለ እንደ ሳኦል ደከመ

፳፩ ሕጻንም ሲሆን በጠብና በሥጋዊ ሰልፈ ጊዜ ዓዋጅ ነጋሪ ለመሰለፍ ያልጨከነ ሰው ሁሉ ከፋ እንደደረጉ ባሮች የተጐሳቈለ ይሁን ሲል በታላቅ ድምጽ ይጮሀል፤

፳፪ እኔም መንፈሳዊውን ገድል በመላ ኃይሌ እጋደል ዘንድ ይገባኛል እነሆ ዓዋጁ ነጋሪ ሃይማኖቴ በመንፈሳዊ ጆሮዬ አደባባይ ቆሞ ለመጋደል ጨክን ይለኛል ብሎ ተመካ። ስለዚህም ነገር አባባል ሕጻኑ ተጋደለ በመኰንኑም ፊት የአቸናፊነት ምርኮን ተካፈለ። ሕጻኑ አበ እመ ማለት ሳያውቅ የደማስቆን ኃይል ይይዛል የሰማርያንም ምርኮ በፋርስ ንጉሥ ፊት ይካፈላል የሚለው የነቢዩ ትንቢት እነሆ ተፈጸመ ኢሳ ፷፡፬

፳፫ መጮህና መደንገጥም በማር ቁርቆስ ደረሰ በመታገሁ ግን ፈጥኖ አጠፋቸው በሁከታቸውም ጠፉ እኒህም ኤልዛቤል ነገ በዚህ ጊዜ ነፍስህን ከእነዚህ እንደ አንዱ ነፍስ ባላደርጋት አማልክት ይህን ያድርጉብኝ ይህንንም ይጨምሩብኝ ብላ በላከችበት ጊዜ የእስራኤል ነቢይ ኤልያስን ያሸሹት ናቸው።

፳፬ ኤልያስም ፈርቶ ተነሣ ነፍሱንም ሊያድን ሄደ በይሁዳም ወዳለው ወደ ቤርሳቤህ መጥቶ ብላቴናውን በዚያ ተወ:: እርሱም በዚያች ቀን በምድረ በዳ ሄደ መጥቶም ከክተክታ ዛፍ በታች ተቀመጠና አቤቱ እኔ ከአባቶቼ አልበልጥምና እንግዲህስ ነፍሴን ውሰዳት ብሎ እንዲሞት ለመነ በክትክታውም ዛፍ በታች ተኛ አንቀላፋም:: እነሆም መልአክ መጥቶ ዳሰሰውና ተነሥተህ ብላ አለው:: ኤልያስም በተነሣ ጊዜ በራስጌው የተጋገረ እንጎቻና በማሰሮ ውኃ አገኘ:: አንሥቶም በላ ጠጣም ተመልሶም ተኛ::

፳፭ የእግዚአብሔርም መልአክ ዳግመኛ መጥቶ ዳሰሰውና የምትሄድበት መንገድ ሩቅ ነውና ተነሥተህ ብላ አለው:: ተነሥቶም በላ ጠጣም:: ኤልያስም በበላው በዚያ ምግብ ኃይል እስከ ኮሬብ ተራራ ድረስ አርባ ቀንና አርባ ሌሊት ሄደ:: ከዋሻም ገብቶ በዚያ አደረ::፩ ነገ፲፱:፪-፱ እነሆ ኤልያስ ይህን ያህል ታላቅ ነቢይ ሽማግሌም ሰው ሲሆን ሞትን ከመፍራት የተነሣ ሸሸ በዚያችም ፍርሀት ምክንያት ተሸሸገ::

፳፮ የማር ቂርቆስ ጽናቱ ግን ጽኑውን መከራ ለመቀበል ይጨክን ዘንድ ግድ አለችው ወንጌልን እንዳስተማረ ሐዋርያው ጳውሎስም ስለራሱ እንዲህ አለ ከክርስቶስ ፍቀር ማን ይለየኛል? መከራ ነውን ችግር ነውን መሰደድ ነውን መራብ ወይስ መታረዝ ነውን ሰይፍ ወይስ ጭንቅነውን?

፳፯ መጽሐፍ ስለ አንተ ቀኑን ሁሉ እንገደላለን እንደሚታረዱ በጎችም ተቈጠርን እንዳለ መዝ ፵፫:፳፪ ነገር ግን እርሱ ወድዶኛልና ሁሉን አቸንፋለሁ ከጌታዬም ከኢየሱስ ክርስቶስ ፍቅር የሚለየኝ እንደሌለ እተማመናለሁ ሞትም ቢሆን ሕይወትም ቢሆን መላእክትም ቢሆኑ የቀደሙትም ቢሆኑ ያለውም ቢሆን የሚመጣውም ቢሆን፣ ኃይላትም ቢሆኑ በከፍታም ያለ ቢሆን በታችም ያለ ቢሆን ልዩ ፍጥረትም ቢሆን የክርስቶስን ፍቅር ሊያስተወኝ የሚችል የለም:: ሮሜ ፲:፴፭-፴፱

፳፰ የሐዋርያት አለቃ አረጋዊ ጴጥሮስንም ልናስታውሰው ይገባናል:: ጌታ ኢየሱስ ደቀመዛሙርቱን በዚህች ሌሊት ሁላችሁም ትክዱኛላችሁ መጽሐፍ እረኛውን እመታለሁ መንጋዎቹም ይበተናሉ ይላልና ከተነሣሁ በኋላ ግን ወደ ገሊላ እቀድማችኋለሁ እንዳላቸው::

፳፱ ጴጥሮስም መልሶ አቤቱ ጌታዬ እኒህ ሁላቸው ቢክዱህ እኔ አልክድህም አለው ጌታ ኢየሱስም እውነት እልሀለሁ በዚህች ሌሊት ዶሮ ሳይጮህ ሦስት ጊዜ ትክደኛለህ አለው::

፴፬ ጴጥሮስም ከአንተ ጋር እሞታለሁ አልክድህምም አለው፡፡ ደቀመዛሙርቱም ሁላቸው እንዲሁ አሉ፡፡ ይህንንም ሲነጋገሩ እነሆ ከአሥራ ሁለቱ መካከል የሆነው ይሁዳ ደረሰ ከእርሱም ጋር ብዙ ሰዎች ሰይፍና ጐመድ ይዘው ከካህናት አለቆችና ከሕዝቡ አስተማሪዎች ዘንድ መጡ አሳልፎ የሚሰጠውም የምስመው እሱ ነው እርሱን ያዙት ብሎ ምልክት ሰጥቷቸው ነበር፡፡

፴፭ ይሁዳም ቀርቦ ሳመውና መምህር ሆይ ሰላም ላንተ ይሁን አለው፡፡ ጌታ ኢየሱስም ወዳጄ መጣህን አለው፡፡እጃቸውንም በጌታ ኢየሱስ ላይ ጭነው ያዙት፡፡ ከዚህም በኋላ ደቀመዛሙርቱ ሁሉ ትተውት ሸሹ፡፡ ጌታ ኢየሱስንም አስተማሪዎችና ጻፎች ወደ ተሰበሰቡበት ወደ ካህናቱ አለቃ ወደ ቀያፋ ወሰዱት ጴጥሮስም እስከ ሊቀካህናቱ ግቢ ድረስ በሩቅ ተከተለው፡፡ ወደ ውስጥም ገብቶ የነገሩን መጨረሻ ያይ ዘንድ ከሎሌዎቻቸው ጋር ተቀመጠ፡፡

፴፮ ከዚህ በኋላ ክርስቶስ ሆይ ትንቢት ተናገርልን የመታህ ማን ነው? እያሉ በፊቱ ምራቅ ተፉበት ራሱን በዘንግ መቱት ፊቱንም ጸፉት፡፡ ጴጥሮስም በግቢ ውስጥ ተቀምጦ ነበር፡፡ አንዲት ሴት መጥታ አንተም ከገሊላዊው ኢየሱስ ጋር ነበርህ አለችው፡፡ እርሱ ግን የምትይውን አላውቀውም ብሎ ካደ፡፡ ወደደጃፍም በወጣ ጊዜ ሌላይቱ አይታው በዚያ የቆሙትን ይህም ከናዝራዊው ኢየሱስ ጋር ነበረ አለቻቸው፡፡ እርሱም ዳግመኛ ካደ ይህን ሰው አላውቀውም ብሎም ማለ፡፡

፴፯ ጥቂትም ቆይቶ ከቆሙት መካከል ጴጥሮስን የገሊላ ሰው ነህና በእውነት ከእርሱ ወገን ነህ ከንግግርህም የተነሣ ትታወቃለህ አሉት እርሱ ግን ይህን ሰው አላውቀውም ብሎ ማለ፡ የንጊዜም ዶሮ ጮኸ፡፡ ጴጥሮስም ጌታ ኢየሱስ ዶሮ ሳይጮህ ሦስት ጊዜ ትክደኛለህ ያለውን ቃሉን አስታወሰ ወደውጪም ወጥቶ መራራ ልቅሶ አለቀሰ፡፡ ማር ፲፬:፳፮:፸፪

፴፰ እነሆ የሐዋርያት አለቃ ጴጥሮስ በጊዜው ሞት ሆይ ማቸነፍ ወዴት አለ? ሥቃይስ ችንካርህ ወዴት አለ? ብሎ በሥጋዊ ሞት እየተዘባበተበት ቁልቁል እስኪሰቀል ሞትን ከመፍራት የተነሣ ካደ፡፡

፴፱ ቂርቆስ ግን ሥጋዊ ሞትን አልፈራም ክርስቶስንም ሊክደው አልወደደም፣ መከራን በመቀበል ብመስለው ከርሱ ጋራ ክብርን በመውረስ እመስለዋለሁ/ሮሜ ፰:፲፯/ አለ እንጂ. ዳግመኛም ይህችንም የዚህ ዓለም መከራ ለዘላለም የማትሆን የዚያችን ክብርና ምስጋና ዋጋ ያህል እንደማያሆን አስባታለሁ አለ፡፡

## ምዕራፍ ፯

፩ ከዚህም በኋላ አንጌናዊው አውሴብና ብረትሠራው ድሜጥሮስ በእግዚአብሔር አመኑ:: መኰንኑም የተመረጠውን ሕጻን ከእንግዳህ ለአማልክቶቹ ሠዋ አልልህም:: ነገር ግን ከዚህ ሥቃይ እንድትድን ከመሥዋዕቱ ሥጋ ብላ ከወይኑም ጠጣ አለው:: ማር ቂርቆስ ግን አይሆንም የረከሰው ወደ አፌ የገባበት ጊዜ የለም አለው:: መኰንኑም ወታደሮቹን አፉን ከፍታችሁ ሥጋና ወይኑን ጨምሩ ብሎ አዘዘ::

፪ ሕጻን ማር ቂርቆስንም አሁን ከአምላክህ ከእግዚአብሔር ዘንድ ያለ ተስፋህ ጠፋ አለው ማር ቂርቆስም አይሆንም እኔ ደስታ ካለበት ከአምላኬ ቤት አልወጣም:: የእግዚአብሔር ጠላት የአጋንንትም ማኅበርተኛ የሰዎችም ጠላት የሆንህ አንተ ግን ከሕዝበ እግዚአብሔር ተስፋ የራቅህ ከእግዚአብሔርም ርስት የተለየህ ነህ:: ይህን ከእግዚአብሔር ዘንድ በፈቃዱ ካደረግሁት ይህን ለራሴ ሳልፈልግ መልካም አድርገህስ ቢሆን የእግዘብሔር መልካሞቹ ሁሉ በተደረጉልህ ነበር:: አንተ ግን በአገልጋዮቹ ላይ ክፋውን ነገር ባደረግኸው መጠን የገሃነማዊ እሳትን ፍም በላይ ከመርህ ለኔ ግን አክሊል ተዘገጅቶልኛል::

፫ መኰንኑም የብረት ጋን አምጡልኝ በውስጡም ፒሳና ሙጫ፣ አረርና ናስ ተይና ብረት አስፈሊጦስም ጨምሩበት እሳቱንም ጢሱ ከሰማይ ደማና በታች እስኪታይ ድረስ አንድዱ አለ:: ወታደሮችም እንዲሁ አደረጉ:: ባለዘይቶችም በጋኑ ውስጥ ዘይት ጨመሩ የጋኑም ግለት በዛ ድምፁም እንደ ክረምት ነጐድጓድ ሆነ እንፋሎቱም እንደ ፀሐይ ያንጸባርቅ ፍላቱም አሥራ አራት ክንድ ያህል ይዘል ነበር::

፬ ያን ጊዜም መኰንኑ በጋኑ ውስጥ የቅዱሳኑን ሞት ሊያዩ አሥራ አንድ ሺህ አራቱን ሰዎች እንዲያመጡአቸው ወታደሮቹን አዘዘ ወደዚያም ሥፍራ አመጡአቸው::

፭ የከበረች ኢየሉጣ ጋኑን ባየችው ጊዜ ከግርማው የተነሣ ፈራች ደነገጠችም:: እግዚአብሔርንም ልትክደው የተጠበቀላትንም መዝገብ ልትተው ወደደች::

፮ ሕጻኑ ቂርቆስም እናቱ እንደፈራች ባየ ጊዜ አላት እናቴ ሆይ ይህን ጋን በማየት አትፍሪ አትደንግጪም የእግዚአብሔርን አምልኮት መተው ትእዛዙንም መተላለፍ ሥጋዊ መቅሠፍትን የነፍስንም ሞት ያመጣብሻልና:: በኖኅ ዘመን የነበሩ ሰዎች በምን ምክንያት በጥፋት ውኃ ጠፉ? በቃየን ሴቶች ልጆች ውበት ተስበው ባደረጉት ዝሙት አይደለምን::

በዚያን ጊዜ ገንዘብን መውደድ አልነበረም ጣዖት ማምለክና የጦርነት ስልፍም አልነበረም ዘፍ ፯:፩-፯

፯ ዳግመኛም የሰዶም አውራጃዎች በምን ምክንያት ጠፋ በላያቸው እስኪተሆለጥንባቸው ና የረከሰውንና የተናቀውንም ነገር እስኪያደርጉ ድርስ የረከሰች ፍትወትን ስላበዙ አይደለምን ዘፍ ፲፱:፩:፴፯ ስለጥፋት ሰዎች ዝሙት ከእስራኤል መካከል ሃያ አራት ሺህ ሰዎች የሞቱ አይደለምን ዘኍ ፳፭:፩-፱

፰ ዳግመኛም አባቶቹ ለእግዚአብሔር የሰጡተ ከማኅፀንም የተለየ እንደ ዘካርያስ ልጅ እንደ ዮሐንስ ልደቱ በመልአክ የተበሰረ ታላላቅ ኃይሎችንና ምልክቶችን ያደረገ ኃያሉ ሶምሶን በምን ዓይነት ምክንያት ከልዑል እግዚአብሔር ራቀ? አመንዝራ በማግባት የነጹ አካላቱን ስላረከሰ አይደለምን? በዚህችም ምክንያት እግዚአብሔር ከእርሱ ራቀ በጠላቶቹም እጅ አሳልፎ ሰጠው:: መሳ ፲፮:፩፴-፩

፱ እንደ ልዑል እግዚአብሔር ልብ የተባለ ከዘሩም የአባቶች ተስፋ ይላክ ዘንድ ክብር ይግባውና ክርስቶስም ዓለምን ሁሉ ለማዳን ከርሱ ወገን ይገለጥ ዘንድ የተገባው ዳዊትም በአንዲት ሴት በማመንዘሩ ተወቀሰ:: እሱም ደም ግባቷን በዓይኖቹ ባየ ጊዜ በነፍሱ የፍትወት ጦር ተከለ

፲ ስለዚህም ሥራ ፈጣሪ በላዩ ላይ ከፍ ከፍ እንዲል እንዲከብርም ገዳይ ከቤቱ አስነሣበት ከጉልበቱ የወጣም አሳደደው ከተጸጸተ ምንጣፉንም እስኪያርስ ድረስ አብዝቶ ካለቀሰ በኋላ ግን እግዚአብሔር የከበሩ አባቶቹን አስቦ በደሉን ይቅር እንዳለው በነቢይ አንደበት ነገረው ፪ነገ፲፰-፲፱፪፪

፲፩ አርባ ዓመት ያህል በቤተመቅደስ ያገለገለ የሸማግሌውን ካህን ቤት በምን ምክንያት ቁጣና ሞት ከደነው? በምክሩ ስላልሄዱ ልጆች አፍኒንና ፊንሐስ ሙተላለፍ አይደለምን እሱስ እንደነርሱ ክፋውን አላደረገም ነገር ግን ከእግዚአብሔር ይልቅ ልጆቹን አብልጦ መውደዱ ስለአምላኩም ክብር አለመቅናቱ በደል ሆነበት እንጂ ፩ ሳሙ ፪:፳፪-፴፮

፲፪ ደኅም እግዚአብሔር ባለጸጋ ወይም ደሀ ቢሆን ሽማግሌም ቢሆን ጕልማሳም ቢሆን ሕግጋቱንና ትእዛዛቱን በሚተላለፉት ላይ ዝም እንደማይል ያመለክታል በሕዝቅኤል እንደተጻፈ በኢየሩሳሌም የታዘዘለትንም ሰው አለው ከመሠዊያው ጀምረህ በማይታይ ሰይፍ አጥፋ ሽማግሌውንና

ጕልማሳውንም አትማር ጻድቅ እንዳይታወቅ በፍርሀትና በመንቀጥቀጥ በፊቱ የሚሄዱ ፈቃዱንም ሊያደርጉ የሚወድዱ እንዳይታወቁ::

፲፫ እነርሱ ግን ወዳጆቹ የርሱም የሆኑት ናቸው:: በጠራ ኅሊና በንጹህም ልብ ትሩፋት እነደሚሠሩ ቅዱሳንም ስሙ ይመስገንና የእግዚአብሔርን መንገድ በተዉ ጊዜ እርሱም ይተዋቸዋል ከፊቱ ያርቃቸዋል ጸጋውንም ከእነርሱ ይወስዳል::

፲፬ በእጅ ጽፈት በብልጣሰር ላይ የሆነውስ መቅሠፍት የአምላክን ታላቅነቱን ተደፋፍሮ አባቱ ከኢየሩሳሌም በማረካቸው የከበሩ ንዋያተ ቅዱሳት ከሚስቶቹና ከመኳንንቱ ጋር ስለጠጣ አይደለምን:: ዳን ፩:፩- ፳፩

፲፭ እንዲህም ከሆነ እናቴ ሆይ ልዑል እግዚአብሔርን ማምለክን አታቃልዪ ከአምላካውያት መጻሕፍት የተሠጠችንንም ትዕግሥት አስተውዪ ከሰይጣናዊ ጣዖት ጋርም ልታመነዝሪ አትውደጂ ከጥንት ለአምላክ ትእዛዝ ማደሪያ ያደረግሽው አካልሽን አታርክሺው እነሆ እንደ ኤልያስና ኤልሳዕ እንደ ደቂቀ ነቢያትም ታላላቅ ድንቆች እንዳደረጉና ከልዑል እግዚአብሔር ጋር ፊት ለፊት እንደተነጋገሩ ደናግልና ቅዱሳን ሁላቸው ከነርሱም በኋላ እንደነበሩ በአዲስ ሕግ ያስተማሩ ነፍሶቻቸውንም ክብር ለሚገባው ለእግዚአብሐር የሠጡ የምሥራች ነጋሪዎች አንድነት እንደሆኑ እንደ ዮሐንስ ድንግልና እንደ ቅዱስ ጴጥሮስ በርሱ ተቀደስሽ፡ ከርሱም ምሥጢራቱን ተቀበሉ ከአንደበቱ የተቀበሉ አሉ ከራእዮቹም የተቀበለ አለ ከራእዮቹም የተቀበሉ አሉ፡ በእርሱና በሰዎች መካከል አስታራቂዎች በዓለም ያሉትንም ወደ መንግሥቱ አጭተው የሚያቀርቡ ሆኑ::

፲፮ በዚህም ምክሩ ሕጻኑ እናቱን ሊያረጋጋ አልቻለም:: ዳግመኛም አላት እናቴ ሆይ ሦስቱን ልጆች ከሚነድድ እሳት ሶስናንም ከአስተማሪዎች እጅ ዳንኤልንም ከአንበሳ አፍ ያደነ እግዚአብሔር እንደሚያድነን እወቂ:: በዚህም ምክሩ ሊመልሳት ባልቻለ ጊዜ በእግዚአብሔር እመኚ ሐዋርያው ጳወሎስንም ዕብራውያን ወደሆኑ ሰዎች ላከው መልእክቱ ያለውን ስሚ አላት::

፲፯ ሃይማኖትስ ተስፋ ለሚያደርጋት የተረዳች ናት የማይታየውን ነገር ተስፋ አድርገው ያመኑ አሉ::

፲፰ በሃይማኖት ለእግዚአብሐር ያቀረበው የአቤል መሥዋዕት ከቃየን መሥዋዕት ይልቅ የተሻለ ሆነ ስለዚህም ጻድቅ እንደሆነ ምስክር ሆነለት፣ መሥዋዕቱን በመቀበል ምስክር የሆነውም እግዚአብሐር ነው ስለዚህም ከሞተ በኋላ እንኳ ተናገረ::

፲፱ ሄኖክ ሞትን እንዳያየው በሃይማኖት ወጣ፣ አልተገኘምም እግዚአብሔር ሠውሮታልና ሳያሳርገውም እግዚአብሔርን እንዳገለገለው መሰከረለት፡፡ ያለሃይማኖትስ እግዚአብሔርን ደስ ሊያሰኙት አይቻልም ወደ እግዚአብሔር የሚቀርብ ሰው አስቀድሞ እንዳለ ለሚሹትም ዋጋ እንደሚሰጣቸው ሊያምን ይገባዋል፡፡

፳ ኖኅም ስለማይታየው ነገር የነገሩትን ባመነ ጊዜ ፈራ ዓለምም በተቀጣ ጊዜ ወገኑን እንዲያድድን ክፍል ያላት መርከብ ሠራ በሃይማኖት የሚገኘውን ጽድቅም ወራሽ ሆነ አብርሃም የተባለው ሰው በሃይማኖት ስማ ርስቱን ያገኝ ዘንድ ወዳለው ሀገርም ሊሄድ ታዘዘ ወዴት እንደሚደርስም ሳያውቅ ሄደ፡፡

፳፩ በሃይማኖትም ከሀገሩ ወጥቶ ተስፋውን ከይስሐቅና ከያዕቆብ ጋር ተስፋ በሰጠው ሀገር እንደስደተኛ በድንኳን ኖረ፣ መሠረት ያላትን ሠሪዋ ፈጣሪዋ እግዚአብሔር የሆነላትን ሀገር ደጅ ይጠኑ ነበርና፡፡

፳፪ እስዋ ሣራም መካን ሳለች ባረጀችበት ወራት ዘር ታስገኝ ዘንድ በሃይማኖት ኃይልን አገኘች ሁለቱም ሰውነታቸው እንደበድን ሆኖ ሳለ ብዛታቸው እንደማይቈጠር እንደ ባሕር አሸዋ እንደ ሰማይ ኮከብ ይሆን ዘንድ ተስፋ የሰጣት እውነተኛ እንደሆነ አምናለችና፡፡

፳ እኒህ ሁሉ አምነው ሞቱ ተስፋ ያደረጉአትንም አላገኙም ነገር ግን ከሩቅ አይተው እጅ ነሱአት፣ በምድር ላይ እነሱ እንግዶችና መጻተኞች እንደሆኑም ዐወቁ፡፡

፳፬ እንዲህ የሚሉ ግን ሀገራቸውን እንደሚሹ ያሳያሉ ከእርስዋ የወጡባትን ሀገር ቢሹ ኖሮስ ወደ እርሷ ሊመለሱ በተቻላቸው ነበር፡፡ አሁን ግን በሰማያት ያለችውን የምትበልጠውን ሀገር ተስፋ ያደርጉ እንደነበር ታወቀ፡፡

፳፭ ስለዚህም እግዚአብሔር አምላካቸው ይባል ዘንድ አያፍርም ተስፋ ያደረጉአትን ሀገር አዘጋጅቶላቸዋልና፡፡

፳፮ አብርሃም በፈተነው ጊዜ ልጁ ይስሐቅን በሃይማኖት ሊሠዋው ወሰደው፣ እግዚአብሔር ከሙታን ለይቶ ሊያስነሣው እንደሚችል አምኖ ስለእሱ አንድ የነበረውን ከይስሐቅ ዘር ይጠራልሀል ብሎ ስለእርሱ ተስፋ ሰጥቶት የነበረውንም አቀረበ፣ ስለዚህ ያ የተሰጠው መታሰቢያ ሆነለት፡፡

፳፪ በሃይማኖት ይስሐቅ ያገኙት ዘንድ ስላላቸው ነገር ያዕቆብንና ዔሳውን ባረካቸው ዮሴፍም በሚሞትበት ጊዜ እስራኤል ከግብጽ የመውጣታቸውን ነገር በሃይማኖት አሰበ ዐጽሙን ትተው እንዳይወጡም በሃይማኖት አዘዘ፡፡

፳፫ ሙሴ በተወለደ ጊዜ በሃይማኖት ሦስት ወር በአባቱ ቤት ሸሸጉት ሕጻኑን መልካም እንደሆነ አይተውታልና የንጉሥንም ትእዛዝ አልፈሩም

፳፬ ሙሴም በሃይማኖት በአደገ ጊዜ የፈርዖን የልጅ ልጅ እንዳይሉት ካደ፣ ለጊዜው ደስ ብሎት ኃጢአት ከሚሆንበት ይልቅ ከእግዚአብሔር ወገኖች ጋር መከራ ሊቀበል ወደደ የክርስቶስ የመስቀሉ ተግዳሮት ከግብጽ ሀብት ሁሉ እንደሚበልጥ ዐወቆአልና፡፡

፴ በሃይማኖት የንጉሥን ቁጣ ሳይፈራ በግብጽ ኖረ፡፡ ዋጋውን ተስፋ አድርጎ ከሚታየው የማይታየውን ሊፈራ ወዶአልና ቸነፈር በኲራቸውን እንዳያጠፋባቸው በሃይማኖት በጉን አረደ ደሙንም ረጨ

፴፩ በሃይማኖት በደረቅ እንደመሄድ የኤርትራን ባሕር ተሻገሩአት፣ ለግብጽ ግን ሰጥመው ሊቀሩ መከራ ሆነችባቸው፡፡ በሃይማኖት ሰባት ቀን በዞሩአት ጊዜ የኢያሪኮ ቅጽር ወደቀ፡፡

፴፪ ረአብ ዘማም ብታምን ከከሐዲዎች ጋር አልጠፋችም ጉበኞችን ተቀብላ በፍቅር ሰውራቸዋለችና፡፡ እንግዲህ ምን እላለሁ የእነ ጌዴዎንን ነገር የእነ ባርቅን የእነ ሶምሶንን የእነ ዮፍታሔን የእነ ዳዊትን የእነ ሳሙኤል እና የሌሎችንም ነቢያት በሃይማኖት የተጋደሉትን ነገሥታቱን ድል የነሡትን መንገዳቸውን ያገኙትን ትሩፋት የሠሩትን ተስፋቸውን ያገኙትን የአናብስትንም አፍ የዘጉትን የእሳትን ኃይል ያጠፉትን ከጦር አንደብት የዳኑትን በመከራቸው የጸኑትን በሰልፍ የበረቱትን የጠላቶቻቸውን ጭፍራ ያሳደዱትን ልነግራችሁ ቀን ያጥረኛልና፡፡

፴፫ ሴቶችም እንደ ትንሣኤ ቀን አስነሡተውላቸው ሙታኖቻቸውን ተቀበሉ ተፈርዶባቸው የሞቱም አሉ፣ የምትበልጠውን ሕይወት ያገኙ ዘንድ ሊድኑ አልወደዱምና የገረፉአቸው የዘበቱባቸው ያሠሩአቸውም ወህኒ ያገቡአቸውም አሉ፡፡ በመጋዝ የሰነጠቁ አቸው

፴፬ በመጋዝ የሰነጠቁ አቸው በደንጊያ የወገሩአቸው በሰይፍ ስለት የገደሉአቸው አሉ፣ ማቅ ምንጣፍ የፍየል ሌጦ ለብሰው ዞሩ ተጨነቁ ተቸገሩ መከራ ተቀበሉ ተራቡ ተጠሙ፡፡ ዓለም የማይገባቸው እነዚህ ናቸው፡፡ ዱር ለዱር ተራራ ለተራራ ዋሻ ለዋሻ ፍርኩታ ለፍርኩታ ዞሩ ሁሉም በሃይማኖት ምስክሮች ሆኑ የሰጣቸውን ተስፋ ግን አላገኙም ያለእኛ

እንዳይገቡ እግዚአብሔር ስለእኛ የምትበልጠውን አስቀድሞ በይኖአልና።

፴፰ ስለዚህም እንደ ደመና የሚከቡን እነዚህ ሁሉ ምስክሮች ያሉንእኛ በመደንገጥ የሚመጣውን መታወክና የፍርሀት ሽክምን ሁሉ ከእኛ እናስወግድ ሃይማኖት ወደሚያስገኝልን ለእኛ ወደሚጠበቅልን ተስፋችንም በትዕግሥት እንገስግስ ኀፍረተ መስቀልን አቃልሎ የታገሠውን ስለሱ ስለተጠበቀው ደስታውም ኀፍረትን የናቀትን በእግዚአብሔርም /አብ/ ቀኝም የተቀመጠውን ፍጹም አምላካችን ኢየሱስ ክርስቶስን እንከተለው። ዕብ ፲፩፡፩፡፭፡፲፩፡፬

## ምዕራፍ ፯

፩ በዚህ ሁሉ ግን ሕጻኑ እናቱን ሊያስጨክናት በአምልኮተ እግዚአብሔርም ሊያጸናት አልቻለም። እንደ እሳት የሚቃጠለውን ጋን ስለፈራችው። ከዚህ በኋላ ዳግመኛ ትዕግሥትን የሚያስረዳት ምክር አመጣ እናቱንም ስሚኝ አላት አውሳጢድ በሚባል ሀገር የሚኖር ስሙ ኢዮብ የሚባል አንድ ሰው ነበረ ይህም ሰው ቅንና ንጹህ እግዘብሔርንም የሚፈራ ጻድቅ ነበረ ሰባት ወንዶችና ሦስት ሴቶች ልጆች ነበሩት ከክፉት ሥራ ሁሉ ይርቅ ነበረ ሀብቱም ሰባት ሲህ በጎች ሦስት ሙቶ ግመሎች አምስት መቶም እንስት አህዮች ነበሩት፣ እጅግም ብዙም አገልጋዮች ነበሩት በጎ ተግባሩም በምድር ላይ ታላቅ ነበር ያም ሰው በፀሐይ መውጫ በምሥራቅ ሀገር ካሉ ሰዎች ይልቅ ቸር ነበረ።

፪ ወንዶች ልጆቹም በአንድነት ሄደው በወትር በእያንዳንዳቸው ቤት ግብዣ ያደርጉ ነበር። ሦስቱ እኅቶቻቸውም ከእነርሱ ጋር ይበሉ ይጠጡም ነበር። የግብዣውም ጊዜ አልፎ ኢዮብ በእግዚአብሔር ፊት ያስተሠርይላቸው ነበር። ማልዶ ተነሥቶም እንደ ቁጥራቸው ስለነርሱ መሥዋዕት ያቀርብ ነበር አንዱን ላም ስለራሱ ኃጢአት ያቀርብ ነበር። ኢዮብም ምናልባት ልጆቼ በእግዚአብሔር ላይ ክፉ ያስቡ ይሆናል ብሎ እንዲሁ ሁልጊዜ ያደርግ ነበር።

፫ አንድ ቀንም የእግዚአብሔር መላእክት መጥተው በእግዘብሔር ፊት ቆሙ ሰይጣንም መጥቶ ከነርሱ ጋር ቆመ። እግዚአብሔርም ሰይጣንን ከወዴት መጣህ? አለው ሰይጣንም ምድርን ዞርኳት ከሰማይም ቤቶች ተመላለስሁ መጣሁም ብሎ ለእግዚአብሔር መለሰ።

፬ እግዚአብሔርም ሰይጣንን በወዳጄ በኢዮብ ላይ የምታስበው እንዳይኖር ዕወቅ፣ በምድር ላይ እንደርሱ ጻድቅና ንጹህ እግዚአብሔርን የሚፈራ ከክፉ ሥራም ሁሉ የራቀ ሰው የለምና አለው።

፭ ሰይጣንም በእግዚአብሔር ፊት እንዲህ ብሎ መለሰ አንተ ቤቱን ሁሉ በውስጡም በውጪውም በዙሪያው ያለውንም መላህለት የእጁንም ሥራ ባረክህለት እንጂ እንስሳውንም በምድርላይ አበዛህለት፣ ነገር ግን እጅህን ዘርግተህ ያለውን ሁሉ ዳስስ በፊትህም ይሰድብሀል፡፡

፮ ከዚህ በኋላ እግዚአብሔር ሰይጣንን እነሆ ያለውን ሁሉ በእጅህ ሰጠሁህ ነገር ግን እሱን አትንካ አለው፡፡ ሰይጣንም ከእግዚአብሐር ዘንድ ወጣ፡፡

፯ እስከዛችም ቀን ድረስ የኢዮብ ወንዶችና ሴቶች ልጆች በታላቅ ወንድማቸው ቤት ይበሉ ይጠጡ ነበር፡፡ መልእክተኛም መጥቶ ጥማድ በሬዎችህን ሲያርሱ እንስት አህዮችህም በአጠገባቸው ሲሰማሩ አደጋ ጣዮች መጥተው ማረኳቸው፡፡ ብላቴኖችህንም በሰይፍ ገደሉአቸው እኔም ብቻዬን ቀርቼ ልነግርህ መጣሁ አለው፡፡

፰ እሱም ሲናገር ሌላ መልእክተኛ መጥቶ ኢዮብን እሳት ከሰማይ ወርዳ በጎችህን አቃጠለች ብላቴኖችህንም በአንድነት በላቻቸው እኔም ብቻዬን ዳንሁ፡ ልነግርህም መጣሁ አለው፡፡ ይህንንም ሲነግረው ሌላ መልእክተኛ መጥቶ ኢዮብን በሦስት ረድፍ የተሰለፉ ፈረሰኞች ግመሎችህን ማረኩ ብላቴኖችህንም በሰይፍ ገደሉ እኔም ብቻዬን ቀረሁ ልነግርህም መጣሁ አለው፡፡

፱ ይህንንም ሲነግረው ሌላ መጥቶ ኢዮብን ወንዶችና ሴቶች ልጆችህ በታላቅ ወንድማቸው ቤት ሲበሉና ሲጠጡ ዐውሎ ነፋስ ከምድረ በዳ ድንገት መጥቶ ቤቱን ከአራት ማዕዘናት ገፋው ቤቱም በልጆችህ ላይ ወደቀ ሞቱም እኔም ብቻዬን ዳንሁ ልነግርህም መጣሁ አለው፡፡

፲ ከዚህ በኋላ ኢዮብ ተነሥቶ ልብሱን ቀደደ የራሱን ፀጉርም ላጨ ከትቢያ ላይ ወድቆ ሰገደ፣ ከእናቴ ማኅፀን ራቁቴን ወጥቻለሁ ራቁቴንም ወደምድር እመለሳለሁ፣ እግዚአብሔር ሰጠ እግዚአብሔርም ነሣ እንደ እግዚአብሔርም ፈቃድ ሆነ የእግዚአብሔር ስም የተመሰገነ ይሁን አለ፡፡ በዚህ ሁሉ ግን በእግዚአብሔር ፊት አልበደለም በእግዚአብሔርም ላይ ከንፈሮቹን ለስንፍና አልሰጠም፡፡

፲፩ ከዚያችም ቀን በኋላ እንዲህ ሆነ፡- የእግዚአብሔር መላእክት መጥተው በእግዚአብሔር ፊት ቆሙ ሰይጣንም ከነርሱ ጋር መጥቶ በእግዚአብሔር ፊት ቆመ እግዚአብሐርም ሰይጣንን ከወዴት መጣህ አለው ሰይጣንም ያን ጊዜ በእግዚአብሐር ፊት ከሰማይ በታች ሄድሁ በምድር

ሁሉ ላይ ተመላለስሁ ወዲህም መጣሁ አለ እግዚአብሔርም ሰይጣንን በውኑ ወዳጄ ኢዮብን ተመለከትኸውን በምድር ላይ እንደርሱ ያለ ገርና እውነተኛ ንጹህም እግዚአብሔርንም የሚፈራ ከክፋትም የራቀ የለምና በከንቱ ገንዘቡን አጠፋ ዘንድ አንተ ብትቀሰቅሰኝም እሱ እስከአሁን ጽድቁን ጠብቆአል አለው፡፡

፲፪ ሰይጣንም መልሶ እግዚአብሔርን ቁርበት ስለቁርበት ነው ሰው ያለውን ሁሉ ስለነፍሱ ቤዛ ይሰጣል፣ ነገር ግን አሁን እጅህን ዘርግተህ አጥንቶቹንና ሥጋውን ዳስስ በፊትህም ይሰድብሀል አለው፡፡
እግዚአብሔርም ሰይጣንን እነሆ ጻድቅ ነፍሱን ተው እንጂ ሥጋውን ሰጠሁህ አለው፡፡

፲፫ ሰይጣንም ከእግዚአብሔር ዘንድ ወጣ ኢዮብንም ከእግሩ እስከ አናቱ ድረስ ክፉ ቁስል ያዘው ገልም አንሥቶ ቁስሉን ያክ ጀመረ፡፡ ከሰፈርም ውጪ በአመድ ላይ ተቀመጠ፡፡

፲፬ ብዙ ጊዜም አልፎ ሚስቱ እስከመቼ ድረስ ትታገሣለህ ጥቂት ጊዜም እጠብቃለሁ ገናም እታገሣለሁ ትላለህ፣ እነሆ ስም አጠራርህ ከምድር ጠፋ ማኅፀኔም በጽኑ ሕመም ታመመ ደከምሁ ለከንቱም መጣሁ አንተም በመግል ተውጠህ በትሎች ተከበህ ትኖራለህ ሌሊቱንም ሁሉ ትዛብራለህ እኔ ግን ከሀገር ወደሀገር ከቤትም ወደቤት እየዞርሁ እቀላውጣለሁ፣ ከድካሜ በእኔ ላይ ካለ ከችግሬም አርፍ ዘንድ ከጧት ጀምሮ ፀሐይ እስክትጠልቅ ድረስ እጠብቃለሁ ዛሬ ግን እግዚአብሔርን ስደብና ሙት አለችው፡፡

፲፭ ኢዮብ ግን አንቺ ከሰነፎች ሴቶች እንደ አንዲቱ ተናገርሽ ከእግዚአብሔር እጅ መልካሙን ተቀበልን ክፋውንስ እንግዲህ አንታገሥምን? አላት ባገኘው ሁሉ ግን ኢዮብ እግዚአብሔርን አልበደለም ኢዮ ፩-፪

፲፮ ከዚህም በኋላ መከራን ለመቀበል የጨከነው ሕጻን ዓይኖቹን ወደ እግዚብሔር አቅንቶ እንዲህ አለ አምላኬ ሆይ ሴት አገልጋይህን ከመጽሐፍህ ውስጥ የምትወጣት ከሆነ በመጽሐፍህ የጻፍከኝ እኔን አጥፋ፣ አቤቱ እይሆንም ይህንን ነገር ፈጽሞ አታድርግ፡፡ አቤቱ እርሻውን አቃጥለህ ፍሬዋን ልትባርክ ትወዳለህን አቤቱ አይሆንም ግንዱ ተቆርጦ ቅርንጫፉ ይጠበቅ ዘንድ ታገዛለህን አቤቱ አይሆንም በስምህ ያመኑት አይተው ሊያድናቸው የሚችል አምላክ የላቸውም ብለው እንዳያስናክሉን፡፡ ዲያብሎስም ከዚህ አሳት በሽሽች ጊዜ ተመክሮ ጠላቶቼ እኒህ ናቸው ዛሬም አቸነፍኋቸው ከመንጋህም አንዲቱን በግ ነጠቅሁ እንዳይል፣ ነገር ግን አቤቱ ለሴት አገልጋይህ የመንፈስቅዱስን ኃይል ስጣት፡፡

፲፯ ይህንንም በጸለየ ጊዜ መንፈስቅዱስ በእናቱ ላይ ወረደ ዲያብሎስም ከእርሷ ሸሸ ከዚህ በኋላ እናቱ የከበረች ኢየሉጣ ለመንግሥተ ሰማያት መርሕ_የሆንከኝ ልጄ ሆይ የሚጠብቀን ገድላችንን እንፈጽም በውስጤ የተሠወረው ወጥቷልና እነሆም ጋኑን በነግህ ከምንጮች ውኃ እንደምቀዳበት ማድጋ ሆኖ አየዋለሁ።

፲፰ ይህንንም እርስ በርሳቸው ሲነጋገሩ ወታደሮቹ ይዘው ወደ ጋኑ ወረወሩአቸው። በውስጡም አንገት የሚቆለምም አንጀትም የሚቆራርጥ መንኩራኩር አለው። ነገር ግን አንዱ እንኳ ቅዱሳኑን አልነካቸውም ጋኑም ማቃጠሉንና መፍላቱን ተወ። ስሙ ገብርኤል የተባለ የእግዚአብሔር መልአክ እንደ ዓይን ጥቅሻ ከሰማይ ፈጥኖ ወርዶ እሳቱን በእጁ በያዘው በትረመስቀል ባርኮ እንደ ነግህ ውኃም አቀዝቅዞታልና። እነሆ ወደ ምድራዊ እሳት ውስጥ መግባታቸው የገሃነም እሳትን አጠፋ፡ በሲና ተራራ በሆነ የሙሴ ሐመልማል አምሳልም የሕይወት እሳት እግዚአብሔርን ተዋሐዱት።

## ምዕራፍ ፰

፩ ቂርቆስም የድርሳን ጸሎት ጀመረ እንዲህም አለ የእግዚአብሔር ቤት በሚሆን በመንግሥት ደጃፍ የዕንቁ መጽሐፍ ሰጠኝ። ጸሎቴም የከበረች ቤተክርስቲያን ናት። ዕንቁውም የእግዚአብሔር ቃል ነው መጽሐፌም መንፈስ ቅዱስ ነው። ጨለማ ወደጸናበትና ብርሃን ወደሌለበት ኮከብና ፀሐይ ጨረቃም ወደማይገኙበት ሀገር ላከኝ። ትርጓሜዋ ለንጳቶስ / / ወደ ሆነ የመጀማሪያቱ ሀገር ደረስሁ በዚያም ከደረታቸው በላይ ሰዎች በእጃቸው ፈረስ ሁለንተናቸው አህያ ከደረታቸው በታች ሰውና አራዊት የሆኑ ሰበድዐትንና ቃግሡተትን አገኘሁ ብዙዎች አጋንንትም ነበሩ እኒህም ሁላቸው ሊገድሉኝ ወደዱ።

፪ መጽሐፌ ግን አሳደዳቸው እኔም ባቢሎን አሸዋ ከሚበዛበት ወንዝ ደረስሁ፣ እንደዕብራውያን ምኩራብ በሰንበት ቀን ካልሆነ በቀር መሻገር የሚችል የለም፣ እኔ ግን በእግዚአብሔር ኃይል በኀሙስ ቀን ተሻገርሁበት። ከጥልቁ ባሕር የሚመጣውም ወንዝ እንዲህ ነው። በውስጡ ውኃ የሚያይ የለም። በወንዙም ተሻግሬ በባሕር ዳርቻ ወዳለች ሀገር ደረስሁ በዚያም ከደረታቸው በላይ ፈረስ ከታችም ፈረስ የሆኑትንና ሰበድዓት ቃግሡታቱንም አገኘሁ ብዙዎች አጋንንትም ነበሩ አሥራ ሦስት ሺህ እባቦች ሦስት መቶ ሰበድዐት ስምንት ሺህ በላይና በታች ደረታቸው የሰው የሆነ አህዮች ቁጥራቸውም የበዛ ክፉዎች አጋንንት ነበሩ።

፫ ይህም እባብ ጅራቱ ከአፉ የሚደርስ ታላቅ ነበር አንድ ብቻውን ሆኖ በጧት ይወጣል በፊቱም ወደጥፋት ጐዳና ይሮጣል ጥርሶቹ የተሳሉ ሰይፎች ናቸው:: ጐኖቹም የወርቅና የናስ አንገቱ የብረት ቅርጽ ጥፍሮቹ የናስ ሆዱ ንጥፍ ደንጊያ ምግቡም ጳ ጺር ነው:: ከፊቱም ከአፍንጮቹም የእሳት ወላፈን ይወጣል::

፬ ዓይኑንም በገለጸው ጊዜ የዮርዳኖስን ወንዝ ይሰበስባል ከዓይኑም አይፈስም:: ከተሳሳተ በኋላ ሴቲቱን ስላሳተ ከመንበሩ የወደቀው ሰይጣን ይህ ነው:: አዳምን ከገነት ያስወጣው እባብ ይህ ነው፣ ወንድሙን እንዲገድል ቃየንን ያስተማረው እባብ ይህ ነው፣ እግዚአብሔር ጥፋትን በምድር ላይ እንዲያመጣ በሰዎች ላይ ክፋትን ያበዛ እባብ ይህ ነው::

፭ የረዐይትን ልብ ያስታበየ ኃጢአትንም ሁሉ ያነሣሣ እባብ ይህ ነው:: የፈርዖንን ሚስት ልብ በእስራኤል ልጆች ላይ ያስጨከነ እባብ ይህ ነው::

፮ የፈርዖንን ልብ ያደነደነ እስራኤልንም የጥጃ ምስል ሠርተው እንዲያመልኩት ያሳሰባቸው እባብ ይህ ነው ዳዊትን በቤርሳቤህ ደም ግባት ያሳተው፣ ሰሎሞንን ከጣዖት ኋላ ኋላ እንዲከተል ያደረገ፣ ሕዝቡ ተመልሰው በኢየሩሳሌም ለእግዚአብሔር እንዳይሰግዱ የወርቅ ጣዖት ይሠራ ዘንድ ኢዮርብዓምን ያሳተ እባብ ይህ ነው

፯ በኤልዛበል ዘመን ኤልያስን ያሳደደ፣ የረከሰውን ጣዖት ሠርቶ በእግዚአብሔር ቤት ውስጥ ያቆም ዘንድ ምናሴን የመራ፣ ጣዖታትንም ሁሉ በዓለም ያስነሣ እባብ ይህ ነው:: ከመጀመሪያ መሳቱ የተነሣ በሰዎች ላይ ባላጋራ የሆነ እባብ ይህ ነው::

፰ ከዚህ በኋላ አየኝ ተከትሎ ሊገድለኝም ወደደ:: በዚያም ጊዜ ጌታዬ ኢየሱስ ክርስቶስ ከቅዱሳን መላእክቱ ጋር ወርዶ እባቡን አቃጠለው የአጋንንትንም ወገኖች ሁሉ አሳደደ ተበትነው የቀሩ እስራኤልን ሰበሰበ በዚያችም ሀገር አደሩ:: የደጃፏም ምልክት ይህች ናት:: ስፋቱ በትልቅ ክንድ ሦስት መቶ ውሳጣዊ አፋም አራት ክንድ የሆነ የብረት ቅርጽ አለው ያም ብረት ሁለንተናው የተጻፈበት ነበር:: በዚያም ሥፍራ የብረት ዱካ አይቀርም በዚያም መሻገር የሚችል ሕያው ነፍስ የለም::

፱ ወደ መንግሥትም ደጃፍ ደርሼ ይህንን ጸሎቴንም ጨርሼ ዲያብሎስ ሸማግሌ ሰው መስሎ በሦስት ዓመት ሕጻን የተሸነፍሁ ወዮልኝ ወዮልኝ እያለ ሊያለቅስ ጀመረ። በዚህ ሕጻን መሳቂያ ሆኛለሁና ወዮልኝ ችንካሮቼን ወዴት እወረውራለሁ? እንግዲህም የማደርገውን ኃጢአት አላውቅም ሽክሞቼ ወደቁ መዝገቦቼም ፈረሱ፡ በዚህ የሦስት ዓመት ሕጻን መሸነፌ የተነሣ በሁሉ ዘንድ አፍሬአለሁና።

፲ ጕልማሳ አሸንፎኝስ ቢሆን ድንቅ ባልሆነ ነበር ነገር ግን ታናሽ ሕጻን አቸነፈኝ እንግዲህ ወደ አረጀው ሸማግሌ ምን ሳደርግ እገባለሁ? እርሱ ይሰማኛልና ይህንንም ዓለም ያየልና ወይስ ቢቻለኝ ወደ ጕልማሳው ልግባን? የቤተክርስቲያን ምሰሶ ጴጥሮስን አናውጽሁ የተጠቀምሁት ግን የለም።

፲፩ ወደጕልማሳም ብሄድ እነሆ ጕልማሳው ጳውሎስ አቸነፈኝ ወደ ታናሽ ሕጻንም ልገባ ብል ከዚህ ሕጻን የሚያንስ የለም ወደ እንስሳም ልግባ ብል እንስሳ ንግግር የለውም።

፲፪ ኃያል ቂርቆስ ከትዕግሥቱ ብዛት በሚያበሩም ተአምራቱ ባቸነፈው ቀን መቸነፋና ውድቀቱ በተገለጠለት ጊዜ የተናገራት ይህቺ የሰይጣን ነገር ክርስቶስ ድል በነሣው ቀን የተናገራትን ፈተኛይቱ ነገሩን መሰለቻት በእንጨት መስቀል ላይ ሳለ ሰይጣን ወደርሱ ቀርቦ ነፍሱን በእጁ እንዳሉ የተጋዙ ነፍሳት ሲየግዛት በወደደ ጊዜ ምስጋና ይሁንለትና ክርክስቶስ ያነ ጊዜ ገሠጸው።
፲፫ የሰማይን ሠራዊትን ሁሉ በመስቀሉ ዙሪያ ደንግጠው አየ። በክፉ ሕመም ተያዘ አብዝቶም ፈራ በጥምቀቱ ቀን በዮርዳኖስ ወንዝ ዳግመኛም በታቦር አብ በግልጥ የመሰከረለት የእግዘብሔር ልጅ መሆኑን ተረዳ።

፲፬ ከዚህ በኋላ ከእርሱ የተነሣ ላብ አላበው በርሱም ምክንያት በነፍሳት መካከል ቆሞ ማናወጥ ሳይቻለው ቀረ ሥራዎቹም ሁላቸው ከጌታችንም ጋር መቃወሙ በፊቱ የተሳሉ ሆኑ።

፲፭ ከዚህ በኋላ እስከወደቀበት ጊዜ ድረስ ጥንት ከመላእክት ጋር የነበሩትን ክብሮች አስታወሰ ከእርሱ ሊወስዳት ሲቻለው የወደደውን ያደርግባት ዘንድ እግዚአብሔር ኃይሉን ተወለት። በአይሁድ አድሮ ያደረገበትን ግብራትም ጁንኳ ልዑል እግዚአብሔር ታገሠ። እርሱ ግን በክፋቱ ተኩራራ። ሰማይና በውስጡ ያሉት ምድርና በላይዋ ያሉትም በፊቱ መቆም የማይቻላቸው ሲሆኑ እርሱ በጲላጦስ ፊት ቆመ ነገር ግን በመጨረሻ ጊዜ እግዚአብሔር ብድራቱን ይከፍለዋል።

፲፯ ከዚህ በፊት የሆነውን ከዚህም በኋላ የሚሆነውን እንተውና ያን ጊዜ ሰይጣን ሥጋን ለብሶ ከሥልጣኔ ያቸነፈኝ ይህ ማን ነው? ከሙታን ተነሥቶ ሲኦልንም ረግጦ በሞቱ ሞትን አጠፋው እስከ ሚለው ድረስ ያለውን ጮኸ:: ከዚህ በኋላ ሰይጣን ድል የቂርቆስ ሽንፈትም በእርሱ ላይ እንደሆነ ባወቀ ጊዜ እንግዲህስ በመኰንኑ ልብ አድሬ ከሕይወቱ እገድለዋለሁ ከዚህም ሕፃን ድካም አርፋለሁ ብሎ ተናገረ::

## ምዕራፍ ፱

፩ ያንጊዜም መኰንኑ የርሱ የሆኑትን በመድኃኒቶቹ ሰይጣንን በፊታችን እንደሚያስለቅሰው አያችሁን ያልሰማነውንም ምሥጢር ነገረን አላቸው::

፪ ማር ቂርቆስም ያን ጊዜ ጸልዮ ቀዝቃዛ ውኃ አፈለቀ አሥራ አንድ ሺህ አራቱን ሰዎችም ረጪቸው የንስሓ ጥምቀትም ሆናቸው::

፫ ከዚህ በኋላ የፈላው ውኃ ከጋኑ ፈሰሰ ከወታደሮቹ መካከል አርባ ያህል ወንዶችን ገደለ መኰንኑም እንጃ በዚህም ውኃ ምትሐት ያደርጋልን አለ:: ወደጋኑም ሊያይ ቀረበ:: ቂርቆስም ሦስት ጣቶቹን ነክሮ በመኰንኑ አንገት ላይ አሳረፈ:: ከአንገቱ ሥጋ ሸሸ::

፬ ያንጊዜም መኰንኑ ሕጻኑን አምላክ እንዳለህ አሁን አወቅሁ አድነኝ ፈውሰኝም አለው:: ቂርቆስም መልሶ በዚህ ነገር ዕድል ፈንታ ርስትም የለህምና አንተ እንደማታምን አውቃለሁ ነገር ግን ስለሚያምኑ ሰዎች እፈውስሀለሁ አለው::

፭ የከበረ ቂርቆስም ጸልዮ የተመለጠች አንገቱን አዳነለት:: እንጌቤናዊው ንዑድ ክቡር ቂርቆስ በሚጣለው ሰው ላይ ይህን ቸርነት አደረገ የከበረ ነቢዩ ሊከብቡት በመጡ ጠላቶቹ ላይ እንዳደረገ፡ ጸልዮ ዓይኖቻቸውን እንዲታወሩ ባደረገ ጊዜ ወደ አሰቃው መርቶ ምግብና መጠጥ ሰጥቷቸዋልና በዚህም ፍጹም ይቅርታውን አስረዳ:: ፪ነገ ፮:፲-፳፫

፮ ከዚህም በኋላ መኰንኑ አንገቱ እንዳዳነለት ባወቀ ጊዜ አንተ አልፋ ሸራፑኤልም አጵሎንና አቴና አርኦያም የተመሰገንህ ነህ ታላቅነትን ለተመላች አርጤምስም ምስጋና ይገባል አንተም የሰማይ አምላክ ክርስቶስ የተመሰገንህ ነህ ብሎ አሰምቶ ተ[illegible] :

፯ ሰማዕት ቂርቆስም አለው የአማልክቶችህ የአጋንንትን ስም መጥራት አስቀደምህን ከዚህም በኋላ ክርስቶስን? ለሁለት ጌቶች መገዛት የሚችል አገልጋይ የለም አልያም እንዱን ይወድዳል ሌላውንም ይጠላል ማቴ ፮፡፳፬ ቡቁዝ ንጉሥ ዘመን የእስራኤል ልጆች እግዚአብሔርን ሳይፈሩት ጣዖታትን ግን እያመለኩ እንደኖሩ እንዲሁ አንተም ልታደርግ ትወዳለህን?

፰ መኰንኑም ካመጣሁብኝ ሥቃይ እንድድን አማልክትን ሁሉ ተማጸንሁ አለው:: ከዚያም ወደ ሌላ ሥፍራ ሄደ በዚያም ሰባ ሰዎች ሊያገላብጡት የማይችሉት ታላቅ የተገጠመ ደንጊያ አገኘ::

፱ መኰንኑም ያን ደንጊያ እንዲከፍቱት አዘዘ:: የቅዱሳኑን ራስ እስከ ጭናቸው ድረስ እንዲችል ውስጡን ሸነቆረው የተሳሉ እርሳስና ናስ ብረትም ገጠመበት በውስጡም ነፍጥ አቆመ በላያቸውም ላይ ቅዱሳኑን አስተኛቸው ወታደሮቹም በጭናቸው ገመድ አሥረው ጐተቷቸው ደንጊያው ወደምድር ተጠጋ እነርሱም በውስጡ አሉ ሲጐትቱአቸውም የቅዱሳኑ ሥጋ ተቆራረጠ የደቃቅ አሸዋም ያህል ሆነ::

፲ ያን ጊዜም የእግዚአብሐር መልአክ ከሰማይ መጥቶ ከዚያ ችግርና መከራ አዳናቸው:: መኰንኑም እነዚህን ሰዎች በስድስተኛው ፍርድ በሰይፍ ካልቀጣኻቸው የሚችላቸው የለም አለ፣ ፈጥነውም እንዲቀጡአቸው አዘዘ::

፲፩ ማር ቂርቆስም በተጠራበት አጠራር ከእናቱ ከኢየሉጣ ጋር ሲጸልይ ያን ጊዜ የጌታ መላእክት ማኅበር በዙሪያቸው ከበቧቸው ጌታችንም ኢየሱስ ክርስቶስ የልባቸውን ሲያውቅ ቃላቸውን ይሰማ ዘንድ ከሰማይ ወረደ::

፲፪ ማር ቂርቆስም መድኃኒታችንን ከመላእክቱ ጋር ሲመጣ ባየ ጊዜ ሰገደለት ጌታዬ ሆይ በቸርነትህ ሁሉን እንደምለምንህ ስጠኝ አለው:: መድኃኒታችንም ማር ቂርቆስን የምትሻውን ሁሉ ለምነኝ እስጥሀማለሁ አለው::

፲፫ ቅዱስ ቂርቆስም አምላኩን አለው ሥጋዬን በምድር አትቅበር በስሜ ለሚለምኑ መታሰቢያዬን ለሚያደርጉ መቅደስህንም በስሜ ለሚሠሩ በሰይፍ በተከለልሁባትም ቀን በዓሌን ለሚያደርጉ ለሁሉም ሰማያዊ ዋጋ አብዛ ጥሪታቸውንም ሁሉ ባርክ ቤቱ በተሠራበት ሥፍራ የከብት እልቂትና ቸነፈር ወደሰው አይቅረብ አባር የውኃም መታጣት አይሁን የእግዚአብሔር ቃል በዚያ ስፍራ አይጓደል ጋኔንም ከ ሥፍራው ይሸሽ ጋኔን ያደረበትም ሰው ወደ ቤቴ ቢመጣ ይፈወስ

፲፩ የገድሌን መጽሐፍ በገንዘባቸው የጻፉና የጻፉትንም በኋላኛው ዘመን ዋጋን ስጣቸው የገድሌን መጽሐፍ ለሚያነብቡም ዋጋቸውን ስጣቸው፣ በስሜ ስጦታ ለሚያመጡ ገንዘባቸውንም ለድሆች ለሚመጸውቱም ያማረውን ዋጋ ስጣቸው:: ስሜንም ጠርቶ ለሚለምን የዕዳውንና የኃጢአቱንም ጽሑፍ አጥፋለት::

፲፪ የሁሉ መድኃኒትም አለው የለመንኸኝን ሁሉ እሰጥሀለሁ አንተ ያላሳሰብኸውንም እሰጥሀለሁ እነሆ በቤትህ ሦስት መቶ መላእክትን አኖራለሁ ትስጠኝ ዘንድ በክርታስ ጽፈው ይሰጡሀል ከሰባቱ ሊቃነ መላእክት ጋር በቀኜ እንደምትቆምም በጉላ በተረዳ ነገር እወቅ

፲፫ እነሆ ሥጋህን በኤልያስ ሠረገላ አኖራለሁ ጉዳና ጠራጊ ከተባለ ከዮሐንስ መጥምቅ በቀር ሴቶች ከወለዱአቸው እንዳተንተ ያለ አልተገኘ ምና:: ክብር ይግባውና መድኃኒታችን ክርስቶስ ይህንን ቃል ኪዳን ሰጠው:: በዚያም ጊዜ አቸናፊ ቂርቆስ በሰይፍ ተከለለ ታላቅ ብርሃንም ሆነ::

፲፬ ገድሉንም በጥር ወር በአሥራአምስት ቀን ፈጸመ:: ኢየሉጣም በዚያች ሌሊት በስድስት ሰዓት ለዓርብ አጥቢያ ተከለለች:: ሕይወትን የሚሰጥ ጌታችን ክርስቶስም የፀሐይ ብርሃን መጠኑ የማይሆንለትን አክሊል አቀዳጃቸው::

፲፭ መኰንኑም አሥራ አንድ ሺህ አራቱን ሰዎች ይገድሉአቸው ዘንድ ወታደሮቹን አዘዘ:: ወታደሮችም እንዳዘዛቸው አደረጉ ቅዱሳኑንም ከገደሉአቸው በኋላ ሥጋቸውን በተኑ የእግዚአብሔር መላእክት ግን ሥጋቸውን ሰበሰቡ መገጣጠሚያቸውንም ሁሉ ጠበቁ ጥር በባተ በአሥራ ስድስተኛው ቀን ተከለሉ::

፲፮ ቂርቆስ የሦስት ዓመት ሕጻን ሲሆን ብዙዎች ሽማግሌዎች ሊጀምሩት እንኳ የማይቻላቸውን ይህን ያህል ገድል እንደምን አበዛ ብሎ ተከራካሪ ቢከራከረን ይህስ ከማርታና ከእንቷ ከማርያም ሥራ ይቆጠራል ብለን እንመልስለታለን:: ከማርታ ሥራ ይልቅ ጌታችን የማርያምን ሥራ አብዝቶ አመስግኗልና:: ማርታ በሥጋዋ ለሥጋ ያውም ለምድራዊ ምሳ አገለገለች ማርያም ግን በመንፈስቅዱስ ለመንፈሳዊ ግብር አገልግላለችና

ይኸውም የእግዚአብሔርን ቃል መስማት ነው። ሉቃ ፲:፴፰-፵፪ ጽድቅም በዕድሜ በመብለጥ አይደለም የክርስቶስም ውድ ከጴጥሮስ ይልቅ ወደ ዮሐንስ መሆን መልእክት ነው። ዮሐ፳፩:፳

፳ የከበረች አ.የሉጣም ከሮም ሴቶች መካከል የተባረከች እንዳትሆን ልጅነቷ አልከለከላትም እንደአረጀች ኤልሳቤጥ ሰማኒያ አራት ዓመት በቤተመቅደስ ውስጥ በጾምና በጸሎት እንዳገለገለች የፋኑኤል ልጅ ነቢይት ሐናም ሉቃ ፪:፴፮ ጸጋን የተመላች ሆነች ሉቃ ፪:፴፮

፳፩ ጽድቅስ በመስጠት ብዛት አይደለም ስለባለ ሁለት ዲናር ከሀብታሞች ሁሉ ይልቅ አብዝታ እንደሰጠች ጌታችን ተናግሯል። ሉቃ፳፩:፩-፬

፳፪ ጾሙና ምጽዋቱ ጸሎቱም ከበዛ ከፈሪሳዊው ይልቅ ቀራጩ ስለ ብዙ ትሕትናው ጸደቀ ሉቃ ፲፰:፱-፲፬ በፈሪሳዊው ስምዖን ቤት ሳለ የበዛ መውደዷን በእንባዋ የገለጠች ኃጢአተኛዋን ሴትም ጌታችን አመስገናት አብዝቶም ወደዳት የበዙ ኃጢአቶቿንም አቃለለላት። ማቴ ፳፮:፮-፲፫

፳፫ በቀኝ የተሰቀለ ወንበዴም በሞቱ ጊዜ ራሱን ወቀሰ በመንግሥቱም በመጣ ጊዜ ያስበው ዘንድ ወደጌታችን ማለደ ገነትንም አደለው ሉቃ ፳፫:፴፱-፵፫

፳፬ ክብር ይግባውና የእግዚአብሔር ጸጋ ከበዛለት ዘንድ የሕጻን ቂርቆስ ገድሉ ብዙ ነው። ሦስቱ ዓመታቱም እነርሱ በፈጣሪና በመላእክቱ ዘንድ ይወደሳሉ ረብ ከሌላቸው ከብዙ ሺህ ዓመታትም ይሻላሉ።

፳፭ እነሆ ማር ቂርቆስ ዘወትር በእግዚአብሔር ቀኝ ቆሞ ስለእኛ ምሕረትን ይለምናል።

የሰማዕቱ የሕጻን ቂርቆስ የገድሉ መጽሐፍ በዚህ ተፈጸመ። የጸሎቱ በረከት የረድኤቱም ሀብት ከወዳጁ ከ ................ ከጥምቀት ልጆችም ሁሉ ጋር ይኑር ለዘላለሙ አሜን።

***************



# ክፍል ፫

## መጽሐፈ ተአምር

አንድ አምላክ በሚሆን በአብና በወልድ በመንፈስ ቅዱስ ስም ለማስመሰጥ ረብ ይሆን ዘንድ በብዙ ጭንቅ ለክርስቶስ ሰማዕት የሆነ የቅዱስ ቂርቆስን የተአምራቱን ዜና እነሆ እንጽፋለን ። የጸሎቱ በረከት የረድኤቱም ሀብት ለዘለዓለሙ ከእኛ ጋር ይሁን አሜን ።

በቅድስት ሀገር በሮሀ ከአምላኩ ዘንድ የክህነትን ሥልጣን የተቀበለ የዓለምን ተድላ ደስታ ንቆ መንግሥቱን ከተወ በኋላ በገዳም ሲኖር ለአርባ ዓመት ያህል በበዓላትና በየሰንበቱ ከሰማይ ኅብስትና ወይን የወረደለት አንድ ጻድቅና ካህን ነበር ። የጽድቁም ምልክት እስካሁን ክቡር ሥጋው ካረፈበት ሥፍራ አለ።

በመንግሥቱ ሳለ በእግዚአብሔር ፈቃድ መንፈስ ቅዱስ ባመለከተው ቦታ በባሕር ላይ ቤተክርስቲያን ሊያንጽ ተነሣ ። ንጉሥ ይምርሐነ ክርስቶስን የቤተክርስቲያኑን መሠረት ለማሳመር ሁሉ እያንዳዱ ደንጊያና ሸክላ እንጨትም እንዲሸከም ትእዛዙን ይነግር ዘንድ በግዛቱ ዓዋጅ ነጋሪ አዞረ። ንጉሥም ከባሕር ዳርቻ ቆሞ አንድ አገልጋዩ በባሕሩ ላይ ለቤተክርስቲያኑ መሠረት ርብራብ ሊያደርግ ከባሕሩ ገባ። ይህንንም ሲያደርግ የባሕር ጋኔን መጥቶ መታው ፈጠኖም ሞተ።



ንጉሥ ይምርሐነ ክርስቶስ የሰይጣንን መተናኰል አይቶ አ ብዝቶ አዘነ። በዚህ ጋኔን ላይ ስለሞተ አገልጋዩ ስለ ቤተክርስቲያንም መታነጽ የማያደርገውን ሲያስብ ስለጽድቅ የተጋደለ ማር ቂርቆስ ድንገት በታላቅ ክብር ተገልጦ የተቀባህ ንጉሥ የክብርህም ካህን ሆይ በእምላኬ ሥልጣን የሞተ አገልጋይህን እኔ አነሣልሃለሁ። ጋኔኑንም እበቀለዋለሁ አንተም ኃይል በተደረገልህ ሥፍራ በምትሠራት መቅደስ ውስጥ በስሜ የተሠየመ ታቦት ታኖ ራለህ አለው። ንጉሡም የክርስቶስ ሰማዕት ሆይ እንዳልከው አ ደርጋለሁ ብሎ መለሰ።

ያን ጊዜም ማር ቂርቆስ እጁን ዘርግቶ የጋኔኑን የራስ ጠጉር ይዞ ከባሕር ውስጥ አወጣው። ቁመቱ ፈጽሞ ረጅም ሁለንተናውም በእሳት እንዳቃጠሉት የእንጨት ግንድ ጥቁር ነበር። ከቅድስት ሀገር ከሮህ ወደ ጎጃም ምዕራብዊ ክፍል እንደደንጊያ ወረወረው በዚያም ሞተ የሞተው አገልጋይ ግን ተነሣ።

ንጉሥም ፈጽሞ ደስ ተሰኘ ። አምስት ጊዜ ከሩቅ የዛጹ እንጨት እየተሸከመ ያችን መቅደስ ሠራት ከአገልጋዮቹም ጋራ ሲሠራ ይውል ነበር። ጌታ ኢየሱስም የመቅደስ ሥራዋን እያመለከተው ከርሱ ጋራ ነበረ። የመቅደስ መታነጽም ከተፈጸመ በኋላ ንጉሥ ይምርሐነ ክርስቶስ በክበረ ሕጻን ቂርቆስ ስም የተ ሠየመ ታቦት በውስጧ አኖረ። ኅብራቸው ባማረ የከበሩ ልብሶችም አስጌጣት በውስጧም በጥቅምት ፲፱ ቀን ቀደሰ ።

ወዳጆቼ ሆይ ሰማዕት ቂርቆስ በእምላኩ ኃይል ለንጉሥ ይምርሐነ ክርስቶስ ያደረገለትን ድንቅ እዩ። ጸሎቱና በ ረከቱ ለዘላለሙ ከእኛ ጋራ ይሁን አሜን ።

## ሁለተኛ ተአምር

የኢየሱስ ክርስቶስ ሰማዕት የቅዱስ ቂርቆስ ተአምር ይህ ነው። ጸሎቱና በረከቱ ከኛ ጋር ይሁን ለዘላለሙ አሜን ።

በሩቅ ሀገር የሚኖር በሕጻንነቱ ለጽድቅ በተጋደለ በቅዱስ ቂርቆስ በረድኤቱ የሚታመን በቃል ኪዳኑ የሚማፀን አንድ መነኩሴ ነበረ። አንድ ቀንም ለሕጻኑ ቂርቆስ ቤት ካህናት ኅብሩ ቀይ የሆነ ቀሚስ ሲሰፋ ድንገት ሰይጣን በልብሱ ጸዳል አምሳል ከሩቅ ታየው። ያንጊዜም የ መነኩሴ ታመመ መብላትና መጠጣትም አቃተው ለሞትም ደረሰ።

በእኩለ ሌሊትም እሱ ወደጌታችን ኢየሱስ ክርስቶስ ከሰማይ የወ ረድህ ከድንግልም የተወለድህ ሆይ አልዓዛርን ከአራት ቀን በኋላ ከመቃብር ያነሣኸው ሆይ አቤቱ እኔንም አንሣኝ የሚሣንህ የለምና ሁሉም ይቻልሀል እንዳንተ ይቅር የሚል አምላክ የለም እንደኔም በምድር ላይ ኃጠአተኛ የለም። እንደይቅርታህ ብዛት መጠን ይቅር በለኝ ለንስሓም የሚሆን ዕድሜ ስጠኝ ። አንቺም እመቤቴ ማርያም ሆይ ፈጽሞ ይቅር ይለኝ ዘንድ ከሕመሜም ይፈውሰኝ ዘንድ ወደልጅሽ ለምኚ ልኝ ። አንተም ተጋዳይ ቅዱስ ቂርቆስ በጠላቴ በሰይጣን እጅ አትተወኝ ብሎ ጸለየ።

ይህንንም ሲያስብና በልቡ ሲጸልይ ዓይኖቹ በእንቅልፍ ከበዱ። ያም ሰይጣን ዳግመኛ ሊያስደነግጠው እግሮቹ ሁለት አንገቱ አንድ ከአንገቱ ላይ ብዙ ራሶች ለራሶቹም አንዲት ዓይን ጆሮ ባለት ሰው አ ምሳል በሕልም ታየው።

መነኩሴውም አይቶ ደነገጠ የሚናገረውንም አጣ:: ያንጊዜም ቅዱስ ቂርቆስ ደም ግባቱ ባማረ ሕጻን አምሳያ ለዚያ መነኩሴ ተገለጠለት:: በብርሃን ግምጃ ተሸልሞ የእጁም ዘንግ በመስቀል ምልክት ነበረ:: ወዳጄን እንዲህ ለሕማም ሥቃይ እንድታሠቃየው ማን ፈቀደልህ ? ብሎ በሚያስፈራ ቃል ሰይጣንን ተናገረው:: ይህንንም ብሎ በእጁ በያዘው በትረ መስቀል ወጋው :: ያን ጊዜ ከመነኩሴው ዓይኖች እስኪሠወር ድረስ እንደንስር በረረ::

መነኩሴውም አንተ አንጌቤናዊው የቅድስት ኢየሉጣ ልጅ ቂርቆስ ነህን አለ :: ቅዱስ ቂርቆስም አዎን እኔ ዘወትር እጠብቅሀለሁ ከአንተም አልርቅም አለው ይህንንም ብሎ ከእርሱ ተሠወረ:: ያም መነኩሴ ከእንቅልፉ በነቃ ጊዜ ፈጽሞ እንዳልታመመ ጤነኛ ሆነ::

ይህ ሁሉ በቅዱስ ቂርቆስ ርዳታ ተደረገለት ከአምላኩ ዘንድ ጸጋን ተቀብሏልና::

ጸሎቱና በረከቱ ከእኛ ጋር ለዘላለሙ ይኑር አሜን ::

## ሦስተኛ ተአምር

በአብና በወልድ በመንፈስ ቀዱስ ስም አንድ አምላክ የሚሆን የሰማዕቱ የቅዱስ ቂርቆስ ተአምር ይህ ነው:: ጸሎቱና በረከቱ ለዘላለሙ ከእኛ ጋር ይሁን አሜን::

አንድ አማኝ ሰው ነበረ:: ሚስቱም መካን ነበረች:: በሀገራቸው በሰማዕቱ በቅዱስ ቂርቆስ ስም የተሠራ ቤተክርስቲያን አለ:: በቀንና በሌሊት ይመላለስ ልጅም ያገኝ ዘንድ አብዝቶ ይለምን ነበር:: አንድ ቀንም ከሚስቱ ጋር ወደ አንድ ራሱን ዝቅ ዝቅ ወደሚያደርግ መነኩሴ ዘንድ ሄደ::

በመንፈሳዊ ሰላምታ ሰላም አላቸው:: ወደእኔ የመጣችሁበት ምክንያት ምንድር ነው አላቸው:: እነሱም አባታችን ሆይ ልባችንን ደስ የሚያሰኝ ከነዘናችንም የሚያረጋጋን ልጅ ስለሌለን ትጸልይልን ዘንድ ወደአንተ መጥተናል አሉት::

ያም መነኩሴ የእኔ ልመና አይጠቅማችሁም እኔ ኃጢአተኛ በደለኛ ም ነኝና ነገር ግን የሕጻን ቂርቆስን አምላክ በሰጠው ቃልኪዳን ተ ማፀኑቅ : እሱም ልጅ ይሰጣችኋል አላቸው:: እነሱም በተጋዳይ ቅዱስ ቂርቆስ ስም ለእግዚአብሔር ስእለት ተሳሉ:: ከዚህም በኋላ ሚስቱ ፀነሰች ወንድ ልጅም ወለደች ስሙንም ወልደ ቂርቆስ
/የቂርቆስ ልጅ / አሉት::

ያም ሰው የቅዱስ ቂርቆስን ገድል ለማጻፍ ገንዘብ ይሰጡ ዘንድ ከሚስቱ ጋር ተማከረ:: ለጸሐፊ ዋጋ የሚሆነውንም ገንዘብ በዚያ መነኩሴ እጅ ሰጡ፡ የቅዱስ ሕጻን ቂርቆስ ገድሉም ተጻፈ :: የገድሉም መጽሐፍ በተመረጠች ስፍራው በተነበበ ጊዜ ያዘኑትን የሚያረጋጋ አ ጋንንትንም የሚገሥጽ ሆነ:: ከአምላኩም ዘንድ ማዕረግን ከሰባቱ የመላእክት አለቆች ክብር ጋር የሚተከከል ክብርን የተቀበለ የቅዱስ ቂርቆስ የኪዳኑ ባሕር እንደተከዚ ሙሉ ነውና:: ጸሎቱና በረከቱ ከእኛ ጋር ይሁን ለዘላለሙ አሜን::

## አራተኛ ተአምር

በአብና በወልድ በመንፈስ ቅዱስ ስም አንድ አምላክ የሚሆኑ የተ ጋዳይ ቅዱስ ቂርቆስና የእናቱ የኢየሉጣ የተአምራቸውን ዜና እጽፋለሁ :: እግዚአብሔር ባረካቸው በትዕግሥትም አጸናቸው:: በስሙ ያመንን እኛንም እንደነርሱ ያጽናን አሜን::

ቴስጣ በሚባል ሀገር በልደቱና በሞቱ ቀን የበዓሉን መታሰቢያ የምታደርግ አንዲት ሴት ነበረች:: ብዙዎች ድሆችን ሰብስባ የስሙ ዜና ስለሚያስደስት ሰማዕት ቂርቆስ የስሙ መታሰቢያ የእግዚአብሔር ወገን ስለሆነች ስለእናቱ ኢየሉጣ የሚያሻቸውን ሁሉ ትሰጣቸዉ ነበር::

ወደርሷ ከሚመጡትም አንዱ ሰው ስለደዌው ለቤተክርስቲያን መባዕ(ስጦታ ) የሚሆን ዕጣን አመጣ:: ያችም ሴት ይህን ስምታ በእራት ጊዜ እንጀራና ጠላ አብዝታ አቀረበችለት:: እርሱ ግን ይህን አ ልወደደም :: ወደዚህም የመጣሁት ስለእንጀራና ጠላ ፍቅር አይደለም ነገር ግን ስለ እግዚአብሔር ሰማዕት ስለቅዱስ ቂርቆስ ለምኑልኝ አለ:: ይህንንም ሲናገር በጥር ፲፭ በበዓሉ ቀን ከሥጋው ደዌ ዳነ ይህን ያዩም አደነቁ እግዚአብሔርንም አመሰገኑት::

ጸሎቱና በረከቱ ከእኛ ጋር ይሁን ለዘላለሙ አሜን::

## አምስተኛ ተአምር

አንድ አምላክ በሚሆን በአብና በወልድ በመንፈስ ቅዱስ ስም የክርስቶስ ሰማዕት የቅዱስ ቂርቆስ ተአምር ይህ ነው:: ጸሎቱና በረከቱ ከእኛ ጋር ይሁን ለዘላለሙ አሜን::

በሮህ ሀገር የሚኖር አንድ ክርስቲያን ሰው ነበር የኢየሉጣ ልጅ የከበረ ቂርቆስን መታሰቢያ ሲያደርግ የወይን መቅጃ ማድጋዎችን ሰበሰቡለት በቤቱም ደጃፍ ሲያጥቡ ውሻ ለከፋቸው የሚባርካቸውም አልተገኘም::

የከበረ ቂርቆስ ግምጃ ልብስ ለብሶ በሌሊት በግልጥ መጣና እኒህን ማድጋዎች ሙሉአቸው እኔ ሦስቱን ልጆች ያዳናቸው የእግዚአብሔር ሰማዕት ነኝ ብሎ ተናገራቸው። ይህንንም ብሎ ተሠወራቸው እነርሱም የኢየሉጣ ልጅ እንደሆነ አውቀው ፈጽሞ ደስ አላቸው። ከእግዚአብሔር ዘንድ በረከትን አውርዶላቸዋልና። በእኒያ ማድጋዎችም በቀዱ ጊዜ የወይኑ ጣዕም አብዝቶ እጅግ የሚደነቅ ሆነ።

ያም ሰው በሕጻን ቂርቆስ ስም ለድሆች ምጽዋት ሰጠ። በዓሉንም ሙብራቶችና ንጹሕ ዕጣን ስንዴና ዘይት መጋረጃም ለቤተክርስቲያን በመስጠት በደስታ አከበረ። ይህም ተአምር በሐምሌ አሥራ ዘጠኝ ቀን በመላእክት አለቃ ቅዱስ ገብርኤል በዓል ቀን ተደረገ ለመጋደል መንፈሳዊ ኃይልን ለዚህ ሕጻን ለሰጠ ለእግዚአብሔር ምስጋና ይሁን ለዘላለሙ አሜን።

** ** ** ** ** **

## ስድስተኛ ተአምር

በአብና በወልድ በመንፈስቅዱስ ስም አንድ አምላክ በሚሆን የሰማዕቱ የቅዱስ ቂርቆስ ተአምር ይህ ነው ጸሎቱና በረከቱ ለዘላለሙ ከእኛ ጋር ይሁን አሜን።

አንጉት በማባል ሀገር የሕጻን ቂርቆስን መታሰቢያ የምታደርግ አንዲት ሴት ነበረች። ጎኔን ታማሚ ያደረገው አንድ ልጅ ነበራት። የእግዚአብሔር ሰማዕት ሆይ ልጄን ፈጥነህ አድንልኝ ሊሞት ደርሷልና እኔም በልደትህና በዕረፍትህ ቀን መታሰቢያህን አደርጋለሁ ብላ የሕጻኑ እናት ተማፀነች። እንዲህም እየተማፀነች የሕጻን ቂርቆስን የልደቱን መታሰቢያ የእናቱ የኢየሉጣንም በዓል አብዝታ አዘጋጀች።

በዚያም ቀን በአምላኬ ስም ከከሀዲዎች አዳራሽ አሳደድሁህ አስወጣሁህም መንፈስ ርኩስ ና ከዚህ ሕጻን ውጣ የሚል ቃል ከወደሰማይ መጣ። በሕጻኑም ያደረው ጋኔን ይህንን ሰምቶ ጮኸ እንዲህም አለ፣ ቀድሞ ይህን ብፈራ ነቢያትን አጠፋሁአቸው ሐዋርያትንም በሮሚ አደባባይ አሰቀልኳቸው። አንተ የናዝራዊ ኢየሱስ ሰማዕት ከጉግዎም አውራጃዎች የምትሳድደኝ ከወዴት መጣህ? አሁንም ሰማይን በዘረጋው ምድርንም በሠራት በጌታችን በኢየሱስ ክርስቶስ ኃይል ተወኝ አታሞፋኝ።

ይህንንም ብሎ ጋኔኑ ከሕጻኑ ወጣ ሕጻኑም ያን ጊዜ ዳነ። እናቱም እግዚአብሔር በሰማዕቱ በኩል ያደረገላትን ቸርነት ዕፁብ ዕፁብ ብላ አደነቀች ድንቁንም ለአንጉት ሰዎች በጉዛምም አውራጃ ነገረች ይህን ድንቅ ያዩና የሰሙም እግዚአብሔርን አመሰገኑት። በጸሎቱ የተቸገሩትን በሚረዳ በዚህ ሰማዕትም ስም በዓል አደረጉ። አገልጋዮቹን ከእሳት ነበልባል ያዳነ እግዚአብሔር በቂርቆስና በእየሉጣ ጸሎትና ምልጃ እኛንም ከኃጢአት ደዌ ያድነን።
የቅዱስ ቂርቆስ ሰማዕት ጸሎቱና በረከቱ ለዘላለሙ ከእኛ ጋር ይሁን አሜን።

** ** ** ** ** **

## ሰባተኛ ተአምር

በአብና በወልድ በመንፈስቅዱስ ስም አንድ አምላክ የሚሆን የክርስቶስ ሰማዕት የቅዱስ ቂርቆስ ተአምር ይህ ነው። ጸሎቱና በረከቱ ለዘላለሙ ከእኛ ጋር ይሁን አሜን።

አንጾኪያ በሚባል ቦታ ከሐዋርያት ማኅበር ጋር በሰማዕቱ በቅዱስ ቂርቆስ ስም ማኅበር የሚጠጡ ብዙ ሰዎች ነበሩ። ከነርሱም ጋር ማኅበር የምትጠጣ አንዲት ነፍሰጡር ሴት ነበረች። የበዓሉም ቀን ሲቀርብ የመውለጃዋ ቀን ደርሶ የምጥ ሕመም ያዛት ፈጽሞም አስጨነቃት እንዲህም ብላ ጮኸች ጌታዬ ኢየሱስ ክርስቶስ ሆይ የጽድቅ ሥራ የሌለኝ ኃጢአተኛ አገልጋይህን እንዳልሞት በይቅርታህ ርዳኝ አንተም የኢየሱስ ክርስቶስ ሰማዕት ሕጻን ቂርቆስ ሆይ በአረማዊ ቤት በለመነህ ጊዜ የመካኗን ልጅ እንደሰማህ የእኔንም ጩኸቴን ስማ ዝናማትን ወደ ምድር ወደሚልክ ሰዎችንም በምስጋና እህል ወደማያጠግብ በፍጥረትም ሁሉ ላይ ይቅርታን ወደሚገልጥ ይቅር ባይ አምላክህ ለምንልኝ ዳግመኛም ከልደትህ በዓል መታሰቢያ ቀርቻለሁና አዝናለሁ።

ይህንንም ጸልያ የፊቱ ወዝ ደስ የሚያሰኝ የበኩር ልጇን ወለደች ስሙንም ወልደ ቂርቆስ አለችው፡ የልደቱንም በዓል ብዙ እንጀራና ዓሣ ብርዝም ለችግረኞች በመስጠት አከበረች። ቤተሰቦቿም ደስ ተሰኙ የእግዚአብሔርንም ምሕረቱን አደነቁ ሕጻን ቂርቆስንም ሥራህ ድንቅ ቀድሞ ካደረግኸውም የሚበልጥ ሆነ ብለው ከፍ ከፍ አደረጉት አምላክን የወለደች እመቤታችን ማርያምንም አመሰገኗት። የሰማዕቱ የቅዱስ ቂርቆስ ጸሎቱና በረከቱ ለዘላለሙ ከእኛ ጋር ይሁን አሜን።

## ስምንተኛ ተአምር

አንድ አምላክ በሚሆን በአብና በወልድ በመንፈስቅዱስ ስም የኢየሱስ ክርስቶስ ሰማዕት የቅዱስ ቂርቆስ ተአምር ይህ ነው:: ጸሎቱና በረከቱ ለዘላለሙ ከእኛ ጋር ይሁን አሜን::

በሮህ ሀገር ወዳለ ወደ ቅዱስ ቂርቆስ ቤተክርስቲያን መገስገስ የምታዘወትር አንዲት ሴት ነበረች:: ከዕለታት አንድ ቀን ከቤተክርስቲየን ደጃፍ ቆማ ስትጸልይ ሰይጣን ባለጸጋ ሰው መስሎ ወደርሷ መጣ ቀርቦም እጅ ነሣት::

ሴቲቱም ከወዴት መጣህ አለችው ሰይጣንም እኔ በዚች ሀገር እኖራለሁ አንቺ ያለዛሬ አተውቂኝምን አላት:: እሷም አምን አላውቅህም ከምርኮ ሀገር የመጣሁ እንግዳ ነኝና አንተስ ወደዚህ የመጣኸው ምን ትሻለህ አለችው:: እሱም ዘወትር በቤተክርስቲያን እየጸለይሁ እኖራለሁ:: እኔ ደወል ደውዬ የሀገሩን ሰዎች በአገልግሎት ጊዜ ለጸሎት እሰበስባቸዋለሁ:: አንቺንም ብዙ ጊዜ ብቻሽን ሆነሽ አየሁሽ እነሆም አገባሽ ዘንድ እንደወደድሁ ልነግርሽ መጣሁ ከድካምም ታረፊያለሽ አላት:: ያስታት ዘንድ ይህንን በሽንገላ ሲነግራት መንፈስቅዱስ ሰይጣን እንደሆነ በኅቡዕ ነገራት እሷም በአብና በወልድ በመንፈስቅዱስ ስም አንድ አምላክ በሚሆን የእግዚአብሔር ጠላቱ መንፈስ ርኩስ ከእኔ ራቅ የሕጻን ቂርቆስ አምላክም ያሳድድህ ብላ ፈጥና በትእምርተ መስቀል አማተበች::

ሰይጣንም የአምላኩን ስም በሰማ ጊዜ እንደ ሰም ቀለጠ እንደጢስም በኖ ጠፋ ሴቲቱም በኢየሉጣ ልጅ አምላክ ደስ ተሰኝች ከጠላት እጅ ፍጽሞ አድኗታልና:: ከዚህም በኋላ የእግዚአብሔር መልአክ ወደርሷ መጥቶ ሄደሽ አግዚአብሔር ስለ ወዳጁ ስለ ቂርቆስ ኪዳን ያደረገልሽን ተናገሪ አላት:: እንዳዘዛትም ለሀገሩ ሰዎች ታየች የተደረገላትንም ሁሉ እንዲህ ብላ ነገረች:: ሰይጣን ሊያስተኝ በሽንገላ ወደ እኔ መጣ አምላኬም ስለ ቂርቆስ ኪዳን አዳነኝ! መንፈስቅዱስ እንዳስተውል ካደረገኝ በኋላ የአምላኬንም ስም በጠራሁ ጊዜ ሰይጣን አፍሮ ከእኔ ሸሸ:: ሕዝቡም ይህንን ሰምተው የሕጻን ቂርቆስ የእቱ የኢየሉጣንም አምላክ በታላቅ ምስጋና አመሰገኑት ይህም ተአምር ከሰሜን እስከ ደቡብ ከምስራቅ እስከ ምዕራብ ተነገረ:: ጸሎቱና በረከቱ ለዘላለሙ ከእኛ ጋር ይሁን አሜን::

## ዘጠነኛ ተአምር

በአብና በወልድ በመንፈስቅዱስ ስም አንድ አምላክ በሚሆን የእንጌቤናዊ ሰማዕት የቅዱስ ተአምር ይህ ነው:: ጸሎቱና በረከቱ ከእኛ ጋር ይሁን ለዘላለሙ አሜን::

ተስጢ በሚባል ሀገር እግዚአብሔርን የማይፈራ ቤተክርስቲያኑንም በትዕቢትና በልቡና ክፋት የማያረካክስ አንድ ቄስ ነበረ:: በዚህ ሰማዕት በቂርቆስ የልደት ቀን ከካህናት ሁሉ ጋር ያገለግል ዘንድ ጓደኞቹ ጠሩት:: እሱም እኔ አልገባም ሌላ የሚያገለግላችሁን ፈልጉ ብሎ መለሰላቸው:: ቀሳውስትና ዲያቆናትም ይህ መሥዋዕት ንጹህ ነው ፈጽመም የከበረ ነው:: በንጽህና የሚቀበለው ይድናል ያለ ንጽህና የማይቀበለውን ግን ጥፋት ያገኝ ዋል እንተም ከተቻለህ ከእኛ ጋር መሥዋዕት ለማሳረግ ግባ ክብርም ይሆንልሀል አሉት:: እርሱ ግን እኔ የክርስቶስን ንጹህ ሥጋ እበላ ዘንድ አይቻለኝም አላቸው:: ይህንንም ያላቸው እንዳያገለግል በሽንገላ ነው የከበረውን የአምላክ ሥጋ ስለማከበር ግን አይደለም::

ይህንንም ሲል የኢየሉጣ ልጅ ሙሴ ስለ እስራኤለ ፍርድ በምድረ በዳ እንዳሰቀለው የናስ እባብ ዘተ ፩፩፰ በሕዝብ ሁሉ ፊት ከምድር ጣለው:: ይህን ተአምር ካዩት እኩሌቶቹ ደስ ተሰኙ፣ እኩሌቶቹ ግን ከምድር የጣለው የበዛ በደል ስለሆነ አለቀሱ:: ይህም ፈጽሞ ድንቅ የሆነ ተአምር በጥር ወር በ ፲፭ ቀን ተፈጸመ:: ከግብጽ እስከ ዐረብ ድረስም ተሰማ:: ጸሎቱና በረከቱ ለዘላለሙ ከእኛ ጋር ይሁን አሜን::

** ** ** ** ** **

## አሥረኛ ተአምር

በአብና በወልድ በመንፈስ ቅዱስ ስም አንድ አምላክ በሚሆን የክርስቱስ ሰማዕት የቅዱስ ቂርቆስ ተአምር ይህ ነው:: ጸሎቱና በረከቱ ከእኛ ጋር ይሁን ለዘላለሙ አሜን::

ሮሀ በሚባል አገር ጽድቅንና መልካም ነገርን የሚወድ እግዚአብሔርንም የሚወድ ወደ ቤተክርስቲያን የሚገሠግሥ ከብዙ መጻለይ ጋር በእንባ መስገድን የሚያበዛ አንድ ንጉሥ ነበረ:: የአባታችን ሆይ ጸሎትን ያዘወትር በየቀኑም ከአንደበቱ አያቋርጥም ነበረ:: በየሰባት ቀኑም ራሱን ለካህን ያስመረምራል:: በዘመኑም ሁሉ እንዲህ እያገለገለ ይኖር ነበር:: ራሱን ይፈትን ዘንድ ኅሊናው የወደደውን በጾጥታ መኖርና ግብረ ቀኖና ይማር ዘንድ የነጹ አባቶችን እየፈለገ ከደብር ወደ ደብር ከዋሻ ወደ ዋሻ ይዞር ነበር:: ምግቡም ቅንጣት እህል ነበር::

አንድ ቀንም ወደ ሰማዕታት ደብር ሄደ:: በዚያም ብዙዎች መነኮሣት አምላካቸውን በጾመና በጸሎት እየተማፀኑ ይኖራሉ፣ ንጉሥም አላቸው

አባቶቹ ሆይ ሥጋን ከማያገዝፋት ነፍስን ግን ከሚያጎሳቁላት የዚህ ዓለም ኑሮ እንደ እናንተ የራቀ ሌላ የለም። እኒያም መነኮሳት እኛም እንዳንተ በመንግሥት ሳለ ስለ እግዚአብሔር ፍቅር በአድባራትና በዋሻዎች የሚዞር አላየንም አልሰማንም አሁንም መልካም ማድረግን አቡነ ዘበሰማያትን መጸለይን አትተው ደግመኛም ከጻድቃን ምስጋና ከመላእክትም ማኅሌት ጋር የሚተባበር የዳዊት መዝሙርን ተማር በዚህም ነፍስህ ትከብራለች። በላይህም ያለው ጸጋ ይበዛልህል አሉት። ንጉሥም አባቶችን እኔም ፍርድ የሌለበትን ከእግዚአብሔርም ጋር የሚያስታርቀኝን ሥራ እሻለሁ አላቸው።

ከዚህ በኋላ ከአባቶች ዘንድ በረከት ተቀብሎ ወደ ቤቱ ተመለሰ በጸጥታ መኖርን ከእህል መከልከልን የሌሊት ሰዓታትን እግዚአብሔርን ለማመስገን በመሰንቆና በእንዚራ ድምፅ የዘመረውን የዳዊት መዝሙርንም ተማረ፣ ሥጋውን አስጨነቃት የዓለምንም ሥራ አጠፋ፣ የነፍሱን ፍለጋ ተከተለ የጌታውንም መስቀል ተሸከመ አስቀድሞ ጌታ በወንጌል የሞቱን መስቀል ያልተሸከመ ሊያገለግለኝ አይችልም እንዳለ። ማቴ ፲፥፴፰

ዳግመኛም የሰውን ሁሉ ሥራ አተረፈ ደግም ሆነ ለድሆች መስጠትንም አበዛ በጾምና በጸሎት ይገዛል ከአባቶችም መጻሕፍትን ተምሮ ሃይማኖትን ያስተምራል። መሥዋዕት ሲያቀርብም እሱም በደሉን ያነጻለት ዘንድ ንጹሁን ቁርባን ይቀበላል። ድሆችንና ስደተኞችንም ፈጽሞ ይሰበስባል። የሰማዕትንም መታሰቢያ በበዓላቸው ቀን ባደረገ ጊዜ ችግር ላለባቸው ወርቅና ብር ይሰጣል፣ የተራቡትን ይመግባቸዋል የተጠሙትንም ያረካቸዋል።

አንድ ቀንም በቅዱስ ቂርቆስ የዕረፍት በዓል በሰማዕታት አለቃ በጊዮርጊስም በዓል አንዲት ሴት የጌታን እናት የእመቤታችን ማርያምን በዓል መታሰቢያ ስታደርግ አገኘ። ፈጽሞ ደስ የሚያሰኝ ይህ ሥራ በእውነት ያድናልን ብሎ ከአባቶች ጠየቀ እምነ በመታመን ያደረገ ከእግዚአብሔር ዋጋውን ያገኛል፡ የጽድቅንም ዋጋ ይቀበላል ጌታ በወንጌል ጻድቁን በጻድቅ ስም የተቀበለ የጻድቁን ዋጋ ይቀበላል እንዳለ። ማቴ ፲፥፵፩

ከዚህ በኋላ ንጉሥ ምስክር በመሆን ገድሉን የፈጸመ የመበለቲቱን ቤት ምሰሶ ያለመለመ ኃያልና ተጋዳይ የሆነ የሰማዕታት አለቃ የጊዮርጊስ መታሰቢያውን ያዘጋጁ ዘንድ አዘዘ። በግዛቱ ያሉትንም ከቅዱስ ቂርቆስ በዓል ቀን ጀምሮ ሰበሰባቸው። መጥቅዕ የሚመቱ ዋሽንትም የሚነፉ መዘመራንም ሁላቸው በከበሮና በጸናጸልም ድምፅ ይዘምሩ ነበር። ሃይማኖትን እያስተማረ ስለ መንግሥት ወንጌል ምስክር የሆነ ሥጋውንም ለጽኑ መከራ ያስጨከነ ሰባ ነገሥታትና መኳንንት ለሰባት ዓመታት በእሳት ያቃጠሉት ሥጋውን የቆረጡት እንደ ትቢያም የበተኑት የእግዚአብሔር ቅዱስ ለሆነ ንዑድ ክቡር ጊዮርጊስ የመታሰቢያ በዓል የተዘጋጀውም ድግስ እጅግ ታላቅ ነበር።

በሬዎች ታረዱ የእንጀራውም ዱቄት ስድስተ ሺህ የተትረፈረፈ የጎሞር መስፈሪያ ያህል ነበር።

ለድሆችና ለስደተኞች ለመጻተኞችም ንጉሥ ቸርነት አደረገ ካህናትና ምእመናንንም ከብዙ ደስታ ጋር ይህንንም በጎ እድል ስለሰጠው እግዚአብሔርን እያመሰገነ ካህናት ምዕመናንን ከቡዙ ደስታ ጋር አጠገባቸው።

ከዚህ በኋላ ከእስራኤላዊት እናታቸው ቤት እናንያና አዛርያ ሚሳኤልም ተብለው እንደተጠሩ እንደ ሶስቱ ልጆች ከእሳት ስላዳነው ስለ ኢየሱስ ክርስቶስ ስም ትዕግስትንና የበዛ መጋደሉ ወዳጃኑ ሕጻን ቂርቆስና ወደ እናቱ ኢየሉጣ ቤተክርስቲያን ሔደ። በደረሰም ጊዜ በዚያ የመልካቸው ባህርይ ልውጥ የሆነ የሰማዕታትን ሥዕል አገኘ። የጳጳሳትንና የሐዋርያወ የጴጥሮስ ሥዕል አለ የእመቤታችን የማርያም ሥዕል ከልጇ ከወዳጇ ከኢየሱስ ክርስቶስ ጋር አለ። የሥላሴም ሥዕል አለ። የአሥራሁለቱም ሐዋርያት የሰባ ሁለቱም ደቀመዛሙርት ሥዕል አለ። በሌላ በኵል በአረሚ ጠብ የተገደሉ የአንጾኪያ ሰማዕታት የቴዎድሮስና የፋሲለደስ ሥዕል አለ። በመካከላቸው ከአባቱና ከእናቱ አብራክ ሳይወጣ አስቀድሞ እግዚአብሔር የባረከው የሕጻን ቂርቆስ ሥዕል ከእናቱ ከኢየሉጣ ጋር አለ። የፊቱ ወዝ ንጉሡን ደስ አሰኘው የልቡም ፍቅረ ተጨመረ።

ንጉሥም ክርስቲያኑን የበዓሉን ቀን ጠየቃቸው እነርሱም የልደቱና የሞቱስ በዓል በጥር በአስራ አምስት ቀን ነው ዳግመኛም በሐምሌ አስራ ዘጠኝ በዓሉ ነው። /ድንግል/ ማርያምን እጅ የነሳት የመላእክት አለቃ የደስታም መለአክ እሱንና እናቱን ከእሳት ነበልባል ስለታደጋቸው ብለው መለሱለት ንጉሥም አለ በጌታዬ በኢየሱስ ክርስቶስ ዘንድ ባለሟልነትን ካገኘሁ ለእበግዚአብሔር የተጋደሉ የቂርቆስንና የእናቱ የኢየሉጣን በዓላቸውን ከእንግዲህ ከድሆችና ከችግረኞች ሀገራቸውንም ንቀው ከተዉ መጻተኞች ጋር አከብራለሁ ጌታ በወንጌል አባቱን እናቱን ሚስቱንና እኅቶቹን ቤተሰቦቹንና ዘመዶቹን ወርቁንና ብሩን እርሻውንም ሁሉ ያልተወ ሊያገለግለኝ አይችልም እንዳለ ማቴ ፤ ፲ ፡፴፯

በዓላቸውን ለሚያከብሩ ስለሱ ክብርን እሰጣቸዋለሁ የታረዙትን በግምጃ ልብስ አስውባቸዋለሁ አምላኩ የሰው እጅ ያልተጠበበትን የጽድቅ ልብስ ይሰጠኝ ዘንድ ለተራቡትም በሕይወቴ ዘመን ሁሉ የተዘጋጀውን ማዕድ እሰጣቸዋለሁ ጌታ በደብረ ጽዮን ከሕይወት ማዕድ ያሳትፈኝ ዘንድ የተጠሙትንም የጠራ ወይን አጠጣቸዋለሁ፡ በመንግሥተሰማያት ከሕይወት ውኃ እረካ ዘንድ። ይህንንም ብሎ በሰላም ወደ ቤቱ ተመለሰ።

የእግዚአብሐር ሰው የቂርቆስ በዓልም በደረሰ ጊዜ ጠጅ ለማድረግ አንድ ሺህ ማሰሮ ማር፣ ሁለት ሺህ ቁና ዱቄት ሦስት መቶም የሰቡ በሬዎችን ያዘጋጁ ዘንድ አገልጋዮቹን አዘዘ:: አገልጋዮቹም እንዲሁ አደረጉ ታላቅ ድግስም ተዘጋጀ:: የእግዚአብሔርን ቃል በሰደበ በእስክንደሮስ አደባባይ መከራን በተቀበለ በቅዱስ ቂርቆስ በዓል ቀንም ድሆችንና ችግረኞችንም ስደተኞችና መጻተኞችን ሰበሰበ ለሁሉም ለእያንዳንዱ መልካም አደረገላቸው፣ ዘማሪዎች በአምላክ ምስጋና ቃል ዘመሩ:: ከሰማይም ታላቅ በረከት በግልጥ ወረደ::

ከተጋበዙትም መካከል ሦስት ተማሚዎች ነበሩ:: ፈጥነውም ከሕመማቸው ዳኑ:: ከእነርሱም አንዱ ለበዓሉ ብዙ እንጀራ ያዘጋጅ ዘንድ ወደ ሀገሩ ሄደ:: ለድሆችም ግብዣ አዘጋጀ:: በዚያም ሌሊት ሕጻን ቂርቆስ በሕልም ተገልጾ ተነሥ እግዚአብሔርም ያደረገልህን ንገር አለው:: ከእንቅልፋም በነቃ ጊዜ ዳዊት አስቀድሞ በመዝሙር በይቅርታህ ተማምኜ በእግዚአብሔር ስም እዘምራለሁ:: እንዳለ መዝ ፲፪:፭ ከፍ ላለ ስሙ እየዘመረ የእግዚአብሔርን ቸርነት ነገረ::

የሮሀ ሀገር ሰዎች ይህን አይተው እግዚአብሔርን አመሰገኑት፣ የክርስቶስን የመከራ ቀንበር ተሸክሞ የእግዚአብሔርን መንግሥት በወርቅ ደሙ የተወዳጀ የጽድቅንም መንገድ ሳይጠራጠር ተከትሎ የድካሙን ዋጋ የተቀበለ ሕጻን ቂርቆስን ከእናቱ ከኢየሉጣ ጋር አወደሱት እኛንም እግዚአብሔር እስከ መጨረሻዋ ሕቅታ ድረስ በቀናች ሃይማኖት ያጽናን:: ጸሎቱና በረከቱ ለዘላለሙ ከእኛ ጋር ይሁን አሜን::

** ** ** ** ** **

## አሥራ አንደኛ ተአምር

በአብና በወልድ በመንፈስቅዱ ስም አንድ አምላክ በሚሆን የኢየሱስ ክርስቶስ ሰማዕት የቅዱስ ቂርቆስ ተአምር ይህ ነው:: ጸሎቱና በረከቱ ከእኛ ጋር ይሁን ለዘላለሙ አሜን::

የቂርቆስና የኢየሉጣን የተአምራቸውንና የመጋደላቸውን ዜና እነሆ እንጽፋለን:: መኰንን እስክንድሮስ በያዛቸው ጊዜ እናቱ የበዛውን ሥቃይ ፈራች:: ቂርቆስም አላት ነፍሶቻችንን የሚያድን ኢየሱስ ክርስቶስ ከእኛ ጋር አለና እናቴ ሆይ አትፍሪ እናቴ ሆይ በእኛ ላይ ሊመጣ ያለውን መከራ አትፍሪ አምላካችን ኢየሱስ ክርስቶስ ስለ እኛ በመስቀል ላይ የተቀበለውን ጽኑ መከራ አስቢ እንጂ እናቴ ሆይ ጽኚ የባቢሎን ንጉሥ ከእሳት እቶን በጨመራቸው ጊዜ መልአኩን ልኮ አናንያንና አዛርያን ሚሳኤልንም ያዳናቸው እግዚአብሐር ከመከራ ሁሉ ያድነን ዘንድ እንደሚችልም አትጠራጠሪ፣ ወደ እግዘብሐር ጸለዪ አምላካችንም የሚሰጠንንም ጸጋና ክብር ተመልከቺ እነሆ የገነት ደጃፍ ተከፈተልን እናቴ ሆይ ይህን የሚያልፈውን መከራ ታግሠን እንግባ::

ሕጻኑም አቤቱ ምድርን በውኃ ላይ ያጸናሃት ጌታዬ ሆይ የእናቴን ልብ አጽና እኔንም አጽናኝ የእስክንድሮስን ማስፈራራት እንዳንፈራ አንተ ሁሉን ማድረግ ይቻልሀልና ኃይልህንም ይቋቋም ዘንድ የሚችል የለምና፣ አገልጋዮችህ አናንያንና አዛርያን ሚሳኤልንም በመልአክህ እጅ ከእሳት የዳንካቸው ሆይ እኛንም ከመከራ ሁሉ እንደምታድነን እምናለሁ ይህንንም መከራ ይሽከም ዘንድ ሥጋችንን አጽና ብሎ በእስክንድሮስ አደባባይ ወደ እግዚአብሔር ጸለየ።

ከዚህ በኋላ መኰንኑ ታጋሹን ሕጻን በለሰለሰ ቃል አንተ ከሕጻናት የምታንስ ሕጻን ሆይ አገዛዜን እመን የአምላክህንና የእናትህን አምላክ ስም ካድ ለበጎ ተግባር ብዙ ወርቅና ብር እሰጥሀለሁ፣ እነሆ በግዛቴ ተገለጥ ለአምላኮቼም ስገድ ከሚያስፈራው የእሳት ነበልባል አድንሀለሁ ልጄና ወራሼም አደርገሀለሁ ነገር ግን አምላክህን ተው አለው።

ሕጻኑም እስክንድሮስን አክሊልን ለመቀዳጀት ብርታቴ እርሱ ነውና አምላኬን አልተውም አለ፣ በሕጻኑም ልመና እናቱ ጸናች። ራሷንም ለሞት አሳልፋ ሰጠች። ከከበረ ልጇ ጋር ሥጋዋን ለእስራኤል አምላክ ሠዋች። አምላካቸውን ተስፋ አድርገው መልአክ ታደጋቸው። ሕዝቡም ይህን አይተው ሕጻኑንና እናቱን የመላእክት አለቃ በሚሆን መልአኩ በገብርኤል እጅ ስላዳናቸው ለእግዚአብሔር ምስጋና አቀረቡ፣ እኛንም ከዚች ዓለም ጥፋት እግዚአብሔር ያድነን።

** ** ** ** ** **

## አሥራሁለተኛ ተአምር

በአብና በወልድ በመንፈስ ቅድስ ስም አንድ አምላክ በሚሆን ጸሎቱና በረከቱ ለዘላለሙ ከእኛ ጋር ይሁንና የሰማዕቱ የቅዱስ ቂርቆስ ተአምር ይህ ነው።

በሮህ ሀገር የሚኖር ጋኔን ያደረበት አንድ ሰው ነበረ። ለጎዣም አውራጃዎች ቅርብ በሆነች በዚያች ሀገር የቅዱስ ቂርቆስ ቤተክርስቲያን ነበረች። በልደቱ በዓል ቀን ብዙዎች ከሩቅና ከቅርቡ ይሰበሰባሉ፡ ዕጣንና የዘይት ቅባት ንጹህ ስንዴ እስከ ኑግ ቅባት ድረስ መባዕ /ስጦታ/ ያመጣሉ ማኅሌት ያደርጋሉ፡ በዚያም በልባቸው ክፋት ያለባቸው በሕዝብ ሁሉ ፊት ይናገራሉ የበዓሉም ቀን ሲቀረብ ወደ ቤተክርስቲያን ሄደው ኃጢአታቸውን ይናዘዛሉ።

ይህም ሰው በበዓሉ ወደ ቤተክርስቲያን ሄደ፣ በመጨረሻም ቀን የቁርባን ጊዜ ሲደርስ ዕጣን በሸተተ ጊዜ ጋኔኑ አሳመመው፣ ራቁቱንም ታየ። ሕዝቡም የሕመሙን ጽናት አይተው ያድነው ዘንድ እግዚአብሔርን ለመኑት።

ርኩስ መንፈስ ውጣ አሳድድሀለሁ ወደ ውጪም አወጣሀለሁ የሚል ቃል ከወደሰማይ መጣ:: ያም ጋኔን ጮኸ በእስክንድሮስ አደባበይ መከራን ለመቀበል ጎሊናዋን ባስጨከነች በእናትህ በኢየሉጣ አቤቱ ተወኝ ምድርን በዘረጋት ሰማይንም ባፀናው አምልሀለሁ አንተ የሃይማኖት ምስክር ነህና የኢየሱስ ክርስቶስ ሰማዕት ሆይ በጸሎትህ ኃየል አታጥፋኝ ብሎ ጮኸ::

በዚህ ሰው ላይ እንዳታድር በፊትህ በመስቀል ምልክት አማትባለሁ የሚል ቃል ለጋኔኑ ተመለሰለት፣ ጋኔኑም በሳተ ቃል ለሕዝቡ እንዲህ አለ የኢየሱስ ክርስቶስ የሆናችሁ ሆይ ፈጽሞ እሳችኋለሁ፣ ነቢያት ወኖቼን ከኢየሩሳሌም አሳደዱአቸው:: ከእነርሱም በኋላ ወንጌልን ያስተማሩ ሐዋርያት በተጠበቀ ፍርድ አዘውትረው አሠቃዩን እኔም በፈቃዴ ሕግ አፍራሾች በሆኑ ነገሥታት እጅ አስገደልኳቸው:: እናንተስ ከእጄ ብታመልጡ በዚህ ሰማዕት ጸሎት ከእግዚአብሔር ዘንድ በላዬ ላይ መቅሠፍት አመጣችሁብኝ ቀድሞ ግን ከኃይሌ የወጣ ከምክሬም ያመለጠ የለም፣ የአለቆችን ምክራቸውን የሚያስት እለኝና፣ ልጄን በሠዋ ጊዜ ነቢዩ ኢሳይያስም ልጅህን አትግደል ባለው ጊዜ የሕዝቅያስን ልጅ ምናሴን ሥጋውን በመጋዝ ይሰነጥቀው ዘንድ አነሣሣሁት ነፍሱን አስገድላት ዘንድ ባይቻለኝም ያን ጊዜ መንፈሴ ደስ ተሰኘች:: ፪ ነገ ፳፩:፲፮ ዕብ ፲፩:፴፯

ካህናት ስምዖንና አልፎምስን መባልሰንም ስለ ክህነትና ስለምስፍና በሊቀካህናት አልዓዛር ላይ አነሳሳኋቸው፣ በእነርሱ ምክር የጽርዕ ንጉሥ አንጥያኮስን በላም መሥዋዕት ምክንያት አመጣሁት የጽዮንን ቤት ቅጥሯን የአንበሳ ልጅ ንጉሥ ሰሎሞን የሠራውንም ሕንጻ ያፈርስ ዘንድ ኃይልን ሰጠሁት፣ የቤተ መቅደስ ገንዘቧን ወርቅና ብሩን የሰንፔር ዕንቁና ኢያስሲዱን አስዘረፍሁ፣ የልዑል ካህን አልዓዛርንም ከሚስቱና አካለመጠን ካደረሱ ሰባት ልጆቹ ጋር አስገደልሁት የመቅደስ ቅጽሯን አፈረስሁ፣ በውስጧም የእርያ መሥዋዕት ይሠው ዘንድ አደረግሁ::

ሕዝቅያስም የጣዖትን መሠዊያ ባፈረሰ ጊዜ ሰናክሬምን አስነሣሁት ጠላቱንም በአምላኩ ኃይል ካሸነፈ በኋላ እጅግ በታመመና ከሟች እስከ ምሽት ድረሥ ሕመም ያዘኝ፣ እንደሚዳ አህያ እንዲሁ እጮሀለሁ እንደ ርግብም እናገራለሁ፣ ዐይኖቼ ደከሙ ወደ ላይ ወደ እግዚአብሔርም ማየት ተሣነኝ ባለ ጊዜ ፈጽሞ ደስ አለኝ ልከራከረውም ከቃሉ ምክንያት ፈለግሁ ፪ ነገ ፳ :፩ - ፯

የእስራኤል ሽማግሌዎች በደንጊያ መወገርን እስኪፈርዱባት ድረስ ከእርሱ ጋር ታመነዝር ዘንድ እንቢኝ ስላለቻቸው በንጽህት ሶስና ላይ በሐሰት

በሐሰት ይመሰክሩባት ዘንድ ሁለቱን አስተማሪዎች አነሣሣሁ፣ ነገር ግን ስለመልካም ሥራዋ የእግዘብሐር መልአክ አዳናት እኔ ግን ጥፋቷን

የባቢሎን ንጉሥ ለወረቅ ምስል ይሰግዱ ዘንድ ሕዝቡን ባዘዛቸው ጊዜ አናንያን አዛርያ ሚሳኤልም ለፈጣሪያችን ካልሆነ በቀር ለማንም አንሰግድም ብለው መስገድን እምቢ አሉ፣ እኔም ከሚያስፈራው የእሳት ሰቶን ይጨምራቸው ዘንድ ንጉሥን አነሣሣሁት ነገር ግን ስሙ ገብርኤል የተባለ መልአክ አዳናቸው ዳን ፫፡፴ ነብዩ ዳንኤልን ከተራቡ አንበሶች ጉድጓድ ባስገባው ጊዜ እኔ ከመከሩት ጋር አብሬ ነበርሁ:: ዳን ፮፡፩፡፳፪

እስራኤልን አርነት ያወጣቸው ዘንድ ሙሴ በፈርዖን ፊት በቆመ ጊዜ እኔ የፈርዖንን ልቡን እያደነደንሁ ነበርሁ ዘጸ ፯፡፲፬ ኢዮብ ስለሥራው በእግዚአብሔር ፊት በከበረ ጊዜ እኔ እግዚአብሔርን ለመንሁት ልጆቹን እስከገድል ከብቶቹንም እስካጠፋበት ድረስ ሁለንተናው እስኪቆስል ሚስቱ እስክትተወው በብዙም ጭንቅ ብቻውን እስኪቀር ድረስ የበዙ ችግሮችን አመጣሁበት:: ኢዮ ፩፡፪

ኤልዛቤል በምክሬ ስለ ወይኑ ቦታ ናቡቴን አስገደለችው ፩ ነገ፩ ፡፲፯ አይሁድም በመልአኩ የምስራች ጌታን በጸነሰችው ጊዜ ዮሴፍ ቢጠይቃት እሷ ካበሰረኝ መልአክ የቃሉ ድምፅ በቀር ሌላ ምንም ምን አላውቅም፣ ስትል ማርያምን ማየ ዘለፋ አጠጡአት /ነገ.ማር/ ቀድሞ ይህን ሁሉ አደረግሁ ዛሬ ግን ምክሬ ላሸች ኀይሌም ደከመ፣ አንተም የኢየሉጣ ልጅ ቂርቆስ በጸሎትህ አሸነፍከኝ፣ ይህንንም ብሎ ጋኔኑ ከዚያ ሰው ወጣ ይህን ሁሉ ያዩና የሰሙትም ሕዝብ የሕጻን ቂርቆስን አምላክ አመሰገኑት:: የቅዱስ ቂርቆስ ጸሎቱና በረከቱ ለዘላለሙ ከእኛ ጋር ይሁን አሜን::

** ** ** ** ** **

## አሥራ ሦስተኛ ተአምር

በአብና በወልድ በመንፈስቅዱስ ስም አንድ አምላክ በሚሆን የቅዱስ ቂርቆስ ተአምር ይህ ነው:: ጸሎቱና በረከቱ የክርስቲያን ወገኖች ከምንሆን ከሁላችን ጋር ይሁን ለዘላለሙ አሜን::

በጎዣም ሀገር አስጨናቂ ደዌ የያዛት የቅዱስ ቂርቆስ የልደቱን ቀን መታሰቢያ የምታደርግ አንዲት ሴት ነበረች:: በኪዳኑም ታምና እግዚአብሔር ከደዌዋ አዳናት፣ እኛንም በከበረ ሰማዕቱ በሕጻን ቂርቆስ ጸሎት ከሥጋና ከነፍስ መከራ ያድነን ለዘላለሙ አሜን::

## አሥራ አራተኛ ተአምር

በአብና በወልድ በመንፈስቅዱስ ስም አንድ አምላክ በሚሆን ቅዱስና ክቡር ስለ አምላኩ ኢየሱስ ክርስቶስም በእውነት የሃይማኖት ምስክር የሆነ የሕጻን ቂርቆስ ተአምር ይህ ነው፡ ጸሎቱና በረከቱ ዘወትር ከእኛ ጋር ይሁን ለዘላለሙ አሜን።

አባቶቼና እናቶቹ ሆይ በጣና ገዳም ያደረገውን እነግራችኋለሁ። በጣና ደሴት ስሙ ኤልያስ የሚባል ዘወትር ለቅዱስ ቂርቆስ ቤተክርስቲያን የሚያገለግል አንድ መነኩሴ ነበረ። ስሙ ፈረሽ ማይሌ የተባለ የእስማኤላዊ የአዳል ንጉሥ የግራኝ የሠራዊት አለቃ ግራኝ እንዳዘዘው ቤቱን በእሳት ያቃጥል ዘንድ ከሰባት መቶ ሠራዊቶቹ ጋር በታንኳ ተሳፍሮ ወደ ባሕር ዳርቻ በደረሰ ጊዜ ይህ መነኩሴ ከሩቅ አይቶ ደነገጠ፣ ወደ ቤተክርስቲያንም እየተቻኮለ ገብቶ እጆቹን በትእምርተ መስቀል ዘርግቶ እያለቀሰ ጸለየ አለም የእግዚአብሔር ቅዱስ ሆይ እንዲህ አታድርግ ይህ እስማኤላዊ ቤተክርስቲያንህን ያፈርስ ዘንድ እንደመጣ ተመልከት፣ ቤትህን በእሳት ያቃጥል ዘንድ አትፍቀድ! አቤቱ አምላክህ በሰጠህ ሥልጣን የጸሎትህን ኃይል አሳይ! የቤትህም አገልጋዮች አይፈሩ አሕዛብም በእግዚአብሔር ስም አይገዳደሩ። ይህንንም ብሎ ሁለት ቀን ሆኖታልና ጥቂት እህል ይቀምስ ዘንድ ወደ በዓቱ ገባ።

ከዚህ በኋላ አርበኛ ቂርቆስ በመንፈሳዊ ፈረስ ተጭኖ መጣ። ሰማዕታትም አለቃቸው ከሚሆን ከሰማዕታት አለቃ ጊዮርጊስ ጋር መጡ። መነኩሴውንም ከቤትህ ግባ ተአምሬንም በአምላኬ ሥልጣን በዚህ ከሀዲ ላይ እንዲህ አሳይሀለሁ አለው። ያንጊዜም በንጉሥ ፊት እንደሚጋደል ወታደር በግልጥ ተዋግቶ አቸነፈው ሙሴ ፈርዖንን እንዳሰጠመው ሕጻን ቂርቆስም በአምላኩ ኃይል ከባሕር አሰጠመው። መነኩሴው ኤልያስም ከርሱም ጋር የነበሩት እግዚአብሔርን በታላቅ ምስጋና አመሰገኑት እያሸበሸቡም ዘመሩ።

የሠመረ ጸሎቱ የተወደደም በረከቱ የክርስቲያን ወገኖች ከምንሆን ከሁላችን ጋር ይኑር ሀገራችን ኢትዮጵያንም ይጠብቃት ለዘላለሙ አሜን።

** ** ** ** ** ** ** ** ** ** ** ** ** ** ** *

የክርስቶስ ሰማዕት የብፁዕ ማር ቂርቆስ የገድሉ መጽሐፍ የተአምሩም ዜና የእናቱም የቅድስት ኢየሉጣ የመጋደሏ ዜና በዚህ ተፈጸመ። ለመጻፍ ላነሣሣን በቸርነቱም ላስፈጸመን ለእግዚአብሔር ምስጋና ይሁን ለዘላለሙ አሜን።

** ** ** ** ** ** ** ** ** ** ** **** ** ** **

# መልክአ ቊርቆስ

ብርሃናዊ ፀሐይ ብርሃኑን እስኪያጨልም ድረስ
መከራን የተቀበልህ ክርስቶስ ሆይ! በመስቀል
የፈሰስ ደምህን ቀለም አድርገህ የመንፈሳዊ
ቊርቆስ የዜናውን መጽሐፍ የመልክአንም
ስላምታ በልቤ ስሌዳ ጻፍ::

ሕጻን ቊርቆስ ሆይ! ትርጉሙ የጣፋጭ ዕፍራን
አበባ ለተባለ የስምህ መታሰቢያ ሰለምታ ይገባል
በሰማያዊ ሥልጣን ነግሦ የሚኖር ይህን ስምህን
በቦታው ሁሉ እንደበቴ በጠራው ጊዜ
ሞት ይደንግጥ ሰይጣንም ይሸሽ::

በራስህ ላይ ለበቀሉና ላደጉ የራስ ጠጉሮችህ
ሰላምታ ይገባል፣ቊርቆስ ሆይ! የሁሉ ጌታ የክርስቶስ
የበረከቱ ሀብት የቅዱስ መስቀሉም ሞገስ
ለዘላለሙ ካንተ ጋር ይሁን በለኝ::

መላ ፊትህ በደም እስኪታለል ድረስ ከነቆዳው
ለተላጨ ጠጉርህ ሰላምታ ይገባል፤ ሕጻን ቊርቆስ ሆይ!
ነፍሴ ከሥጋዬ ተለይታ በምትወጣ ጊዜ
ከሰማይ ወደ እኔ ስትመጣ የራስህን ዘውድ
በራሴ ላይ አኑር::

ከፀሐይና ከጨረቃ ብርሃን ሰባት እጅ ለሚያበራ
ፊትህ ሰላምታ ይገባል፤ ለዘላለም ደስ ብሎህ
የምትኖር ሕጻን ቊርቆስ ሆይ! ኖኅን መርከቡ ከጥፋት
ውኃ እንዳዳነችው ጸሎትህ ከልቅሶና ከዋይታ ታድነኝ::

ከላይ በታች ላሉ አራቱ ቅንድቦችህ ሰላም እላለሁ፤ የክርስቶስን ሕማሙንና ሞቱን የተናገርህ ሕጻን ቂርቆስ ሆይ! ሁሉ ለቤቱ ተግቶ ያስባልና አቤቱ በከንቱ እንዳትጠፋ ቤተመቅደስህን ለመጠበቅ ትጋ።

በመማለል ወደ ላይ ተሰቅለው የብረት ችንካር ነበልባሉን አይተው ሳይደነገጡ ዓይኖችህ ሰላምታ ይገባል፤ ሕጻን ቂርቆስ ሆይ፤ ጽድቁንና የበዛ ይቅርታውን እንዲሰጠኝ በፍጹም ልብህ የታመንኸበት አምላክን ዘወትር ስለእኔ ለምነው።

ያለፍርሀትና ያለማፈግፈግ የሁለት ችንካሮችን ሕማም ለተቀበሉ ጆሮዎችህ ሰላምታ ይገባል፤ የድንግል ማርያም ታማኝ የመንፈስቅዱስም ወዳጅ ቂርቆስ ሆይ! አገልጋይህ ከበደል ውድቀት በትንሣኤ እስከነሣ ድረስ ሦስት ሰብዔ ጸልይልኝ።

ከዐላዊ መኮንን እጅ ብዙ ጊዜ መጸፍትን ለተቀበሉ ጉንጮችህ ሰላምታ ይገባል፤ /ቂርቆስ ሆይ/ ሰይጣንን የሚያሸሽ ሞትንም የሚያስደነግጥ የአብና የወልድ የመንፈስ ቅዱስንም ስሞች በግምባሬ ላይ ጻፍልኝ ምልክትም አድርግልኝ።

የዐመፃ ማኅበሮች እጆቻቸውን ዘርግተው ሰናፍጭና ጨው በውስጣቸው ለጨመሩባቸው አፍንጫዎችህ ሰላምታ ይገባል፤ ሽንጋይ የሥጋ ሽቶን ያቸነፍህ ሕጻን ቂርቆስ ሆይ! የፈሰሰ ደምህን የተቸነከረ አካልህንም አይቶ እሱ እግዚአብሔር ገነትን ከፈተልህ።

እንደ መላእክት ምስጋናን ለሚናገሩ ደስ ለተሰኙ
ከንፈሮችህ ሰላም እላለሁ፤ የእስጢፋኖስ ወገን የሰማ
ዕቱ ሚናስም ባልንጀራ ቂርቆስ ሆይ ነበልባል ጸሎትህ
እሳት ልመናህም የኃጢአቱን እሾህ ሁልጊዜ ያቃጥልልኝ

ጥበብና እንደበትን ከፈጣሪ መንፈስቅዱስ ለተቀበለ
አፍህ ሰላምታ ይገባል አእላፍ ከሀዲዎችን ያቸነፍህ
ሶምሶን ቂርቆስ ሆይ! በጎሊናዬ ማሳ በቅሎ ያደገ
ስንፍና በሥልጣንህ በትእዛዝህም ማጭድ ይቆረጥ፡፡

ንጻታቸው እንደበረዶ መልካቸውም እንደመረግድ (ዕንቁ)
ለሆነ ጥርሶችህ ሰላምታ ይገባል የእግዚአብሔር ወልድ ወዳጅ
ቂርቆስ ሆይ በጎሊናዬ ማሳ በቅሎ ያደገ ስንፍናን
በሥልጣንህና በትዕዛዝህ ማጭድ ይቆረጥ፡፡

በመድኃኒተኛ እጅ ከግንዱ ለተቆረጠ ምላስህ
ሰላምታ ይገባል፤ የጋኑ ነጉድጓድ ያላስፈራህ ቂርቆስ ሆይ!
አብርሃም ይስሐቅ ልጁን እንደባረከው አንድነታችንን
/አያንዳንዳችንን/ ዛሬ ባርክ፡፡

ከአፈር ተፈትኖ እንደወጣ የጠራ ብር ከነውር
ለንፃ ቃልህ ሰላምታ ይገባል፤ የጥበበኞች ጥበበኛ
ከዐዋቂዎችም ይልቅ ዐዋቂ የሆንህ ቂርቆስ ሆይ!
ከሰማዕት እስጢፋኖስና ከተወደደ ሚናስ ጋር
በባሕር የታነጸች መቅደስህን ጎብኛት፡፡

እንደ በረከትና የደቅርጋ ነፋስ መዓዛው ለማያስመልም እስትንፋስህ /ትንፋሽህ/ ሰላምታ ይገባል፣የምስራች ነጋሪ ቅዱስ ወንጌልንም ያስተማርህ ሕጻን ቂርቆስ ሆይ! በድንግል ማርያም ልጅ መስቀል /እግዚአብሔር/ይሰማህ በሚል

በንጉሥ ዳዊትም ቃል እኔን ባርከኝ።
የሁሉን ልመና ስምተህ የምትራዳ ቂርቆስ ሆይ!
ለጉረሮህ ሰላምታ ይገባል፣ ከገዳይ ከግፈኛም ሰው
ያድነኝ ዘንድ በምትጠቅም ጸሎትህ የሚያይ እርሱ
ግን የማይታይ እግዚአብሔርን ዘወትር ለምነው።

በአሳታዊ ሰይፍ እንደበት እጎንብሶ ለተቆረጠ
አንገትህ ሰላምታ ይገባል፣ ሕጻን ቂርቆስ ሆይ፣
ከዝንጉ እስክንድሮስ ከከሀዲዎች ጭፍራዎቹም ዘንድ በየጊዜው ያገኘህን
መከራና ችግር ስንቱን እናገራለሁ፣

የፈጣሪ የወልደማርያምን ቀንበር መስቀልን የተሸከመ ትከሻህን ሰላም
እላለሁ፣ ቂርቆስ ሆይ! ደስ ያለው የምሥራች ነጋሪ መልአክ ገብርኤል
ከአንተ ጋር ይቅርባይ በሆነ አምላክ ፊት ቆሞ ኃጢአቶቼን ያቃልልኝ፣
በደሌንም
ያስተሥርይልኝ።

ክርስቶስ በሦስት ሰዓት እንደተቀበለ ብዙ ግርፋትን
ለተቀበለ ጀርባህ ሰላምታ ይገባል፣ ቂርቆስ ሆይ
የሦስት ዓመት ልጅ ስትሆን ጽኑውን ድብደባ እንደምን
ቻልከው፣ የሚባላው እሳትስ እንደምን አላስፈራህም?

መጽሐፍ እንደማያመሰግነው እንደ ሰገራ ልቡና ለከበደው ደረትህ ሰላምታ ይገባል፣ ሕጻን ቂርቆስ ሆይ! ከእናትህ ጋር በአንድነት እቶኑን እንደ ጤማ የረገጠው እሳቱንም እንደውኃ ያቀዘቀዘው እንዳንተ ያለ ማን ነው?

የሊቅ/አለቃ/ ክርስቶስ የሰላሙና የጽድቁ ማኅበሮች በላይ ለተቀመጡበት ጭንህ ሰላምታ ይገባል፣ ሕጻን ቂርቆስ ሆይ! ቀድሞ የኤፍሬም ልጆች እንደተገለበጡ በትእዛዝህ ቃል ጠላቶቹ በየጠዋቱ ይገልበጡ ባላጋራዎቹም ይውደቁ።

በሥቃይና በድካም ስለንስለት ለቆሰሉና ለደከሙ እጆችህ ሰላምታ ይገባል፣ የሰማይ ንጉሥ የክርስቶስ ወታደር ኃያሉ ቂርቆስ ሆይ! ስሟ የጣፈጠ የቡርክት ማርያም በረከቷንና ሰላሟን እንድቀበል ርዳኝ።

ከሾለት ለጿት ወርቆችህ የምስክርነት ደምን ለተረጩ ክርንህም ሰላምታ ይገባል፣ ቂርቆስ ሆይ ይቅር በለው ብለህ የሚራራ እግዚአብሔርን ስለእኔ ማልደው።

የእግዚብሔርን ፍቅር ለያዙና ለዳሰሱ ክንድህና ለመዳፍህ በአንድነት ሰላምታ ይገባል፣ ጥበብና ዕውቀትን የተመላህ አስተዋዩ ሕጻን ቂርቆስ ሆይ! አቤቱ የእንደበቴን ነገር ፈጥነህ አሳርግ የአፌንም ምስጋና አሳስብ።

እሥሩ ጣቶችህን ከጥፍሮቻቸው ጋር ሰላም
ሰላም ሰላም እላቸዋለሁ፤ ዋናተኛ ቂርቆስ ሆይ!
ጤግሮስ ልቅሶና ግዮን ኀዘን እነሆ በዚህ ዘመን
ኀሊናዬን እስጥመውታልና ፍጹም ፀጥታ
ወዳለበት አሻግረኝ።

ለቀኝ ጎንህ ዳግመኛም ለግራ ጎንህ
ሰላም እላለሁ፤ በአካል ሕጻን በጥበብ
ብዛት ግን አረጋዊ የሆንህ ቂርቆስ ሆይ
ቀድሞ ዕብራዊው ሙሴ ግብጻዊውን ሰው
እንደገደለው ጠላቴን /ሰይጣንን/ ፈጥነህ አጥፋው

የመከራ የሥቃይ እንጀራን ራት ሳደረጉ
ሆድህና ልብህ በአንድነት ሰላምታ ይገባል፤
ቂርቆስ ሆይ! የአፌን ቃል የተወደደ አድርግልኝ፤
የለመንሁህንም ብዙውን ነገር ለአምላክ አሳስበው
ዘወትርም ንገረው።

ከበቀልና ከቂም ለራቁ ኩላሊትህና ኅሊናህ
ሰላምታ ይገባል፤ ተአምረኛው ቂርቆስ ሆይ! ምልክዓም
እንደተባለ እንደሙሴ ፈርዖን ኃጢአቴን በሚያስጥም
የሥርየት ባሕር ወርውረው አስጥመውም።

በሰማይ ሆድህ መካከል ለተሰቀሉ (ላሉ)
እንጀትህና ሆድዕቃህ ሰላምታ ይገባል፤ ጨለማ
ክህደትን የምታስወግዳት ፀሐይ ቂርቆስ ሆይ! የእናትህን
ቀጸላ በራሴ ላይ አዙር፤ የእናትህ የኢየሉጣንም አክሊሏን ስጠኝ።

በአንደትና በልብ መካከል ያለች አንዲት እንብርትህን
ሰላም እላለሁ፤ ሕጻኑ ቂርቆስ ሆይ! ለሚች በግህ
ከዚህች ዘመን መከራ ከበዛ የእሳት ሰይጣንም
ሥራው ጠባቂ ሁነኝ።

ዝናር ሃይማኖቱን ታጥቆ የገገር እስክንድሮስ
ወሮቹን ለቀጠቀጠ ወገብህ ሰላምታ ይገባል፤
ለቲቶ መምህር ለጳውሎስ ወገን የሆንህ ባለሽቱ ልሳን
ቂርቆስ ሆይ! ለንጉሥ ሠራዊቱን ለእረኛም መንጋውን
ይጠብቅ ዘንድ እምላክን ማልደው ይቅርታውንም ለምን።

በጥበበኛ አንጥረኛ እጅ ለተሠራ ለአጽሉን ሳልተገዙ
ጭኖችህና ጉልበቶችህ ሰላምታ አቀርባለሁ
ቂርቆስ ሆይ! ክፋቷ የማያልቅ የመሬታዊት ሥጋዬ በደሏን
ፈጽሞ ይቅር ይል ዘንድ ስለ ድንግል ማርያም ክርስቶስን ማልደው

የቀያፋ ባላንጀራ በሆነ በእስክንድሮስ አደባባይ መታሠርን
ለተቀበሉ እግሮችህ ሰላምታ ይገባል፤ የመንፈስቅዱስ
ልጅ የሳውልና የኬፋም ወንድም ቂርቆስ ሆይ! ማኅበሮችህ፤
ከአንተ ጋር ስለገድላቸውና ትዕግሥታቸው እልፋ በተባለ
በክርስቶስ ፊት ተስፋን አገኙ።

በሥቃይ ጎዳና ለተመላለሱ ተረከዝህና
የውስጥ እግርህ በምስጋና ሰላምታ ይገባል፤
ቂርቆስ ሆይ! አንተ ሀኬተኛ አገልጋይ፣ መከፉን
ኃጢአትና መስፍን በደል ለዘመናት የገዙህ
ይበቃል ብለህ አርነት አውጣኝ።

የሶምቃይ ዐጸድን የመከራንም ቦታ ለረገጡ
ጣቶችህና ጥፍሮችህ ፈጥኙ ሰላምታ አቀርባለሁ፤
ብርሃንን የተጎናጸፍህ ሙሽራው ቂርቆስ ሆይ! በምድርና
በሰማይ እኔ ሳለሁህ ልጄ ሆይ ስለምን ኀዘንን ታበዛለህ ቢለኝ።

ቅላቱ እንደ ሮማን ቅላት ለሆነ በምድር ለሚያቅላላ
በሰማይም ለሚያበራ ቁመናህ ሰላምታ ይገባል፤ ሕጻን
ቂርቆስ ሆይ! እንደወደድከኝ እረዳበት ዘንድ ልቤ
በሚሻው ልክ የሦስቱን አካላት /የሥላሴን/ በረከት በንግግርህ ስጠኝ።

በዮርዳኖስ ውኃ ለተጠመቀ የሰላምና የእርቅ ቅባት
ሜሮንንም ለተቀባ መልክህ ሰላምታ አቀርባለሁ፤ ቂርቆስ ሆይ! ሠለስቱ ደቂቅ
እሳቱን እንዳቀዘቀዙ፤ በነኀድጓድ! ጸሎትህና በመብረቅ ልመናህ የሚቀጣጠል
የእሳቱን እቶን ነበልባል አቀዘቀዝህ።

ከሀዲ መኮንን ሥጋህን በገደለ ጊዜ ሊገድላት ላልቻለ ለነፍስህ መውጣት ሰላምታ
ይገባል፤ ቂርቆስ ሆይ፤ የሰመንሁህን ልመና ሰምተህ ከሁሉ ይልቅ ሲእልን
አፈራለሁና በወንጌል እናር ዘንድ ከጽድቅህ ጽድቅን አድልኝ።

ለእምላክ ሕግ በቀና በኤልያስ ሠረገላ ተሰውሮ
ላለ ሥጋህ ሰላምታ ይገባል፤ ለኀጢአተኛ የምትማልድ
የእስተማሪዎች አስተማሪ ቂርቆስ ሆይ! በመስቀል ላይ
በተሠዋ /ራሱን በሠዋ አምላክ/ዘንድ መተላለፌን አስሥርይልኝ በደሌንም
በየሰባቱ ሰባ ጊዜ አስቀርልኝ።

እንደርገኑን ክርስቶስ መገፋት ልብን ለሚያስለቅስ መከራህና የበዛ መገፋትህ ሰላምታ ይገባል፤ የደስታዬ ክረምት ቂርቆስ ሆይ! የልቅሶና የዋይታ ሰው በምሆን በእኔ ላይ ለሦት ወራት ያህል የደስታ በረከትህና የንጹህ ዝናም ነጠብጣብ ያንጠባጥብ።

የመከራው ዜና በሚያስደነግጥ በመስቀሉ በግ በክርስቶስ ደም ስተረጨ ለደምህ ምንጭ ሰላምታ ይገባል፤ የሰማዕታት ወንድም የሐዋርያትም ልጃቸው ቂርቆስ ሆይ! መታሰቢያህን ለሚያደርጉ የመንፈስቅዱስን ስጦታ ስጣቸው ከአምላክም ዘንድ የጽድቅን ዋጋ አዘጋጅላቸው።

እሳታውያን በሚሆኑ ሰባቱ ነገድ መካከል ለሆነ አኗኗርህ ሰላምታ ይገባል፤ ቂርቆስ ሆይ! ቤትህ በታነጸበት በእንተም ዐጸድ የሚገድል ቸነፈር ለዘላለሙ እንዳይመጣ በአብና በወልድ መንበር ፊት አማልድ።

ላማረ ቁመናሽ በመንፈስ ቅዱስ ሰላምታ ሰላምታ ይገባል፤ መዐዛሽ የጣፈጠ ገነት ኢየሉጣ ሆይ! ዝናም ከደመና እንደሚፈስስ የጡቶሽ ወተት ዛሬ በአፌ ውስጥ ይፍሰስ።

ለአርባ ሦስት መልኮችሽ ለአራቱም ባሕርዮችሽ ሰላምታ ይገባል፤ የቂርቆስ እናት የከበርሽ ኢየሉጣ ሆይ! በከንቱ እንዳልጠፋ ምሕረቱ የበዛ የጽድቅ አምላክ እግዚአብሔርን ስለእኔ ለምኚው።

ይህን የማንሌት ቃል ይህንንም ድርሰን በአይ
የጻፈውን በእንደበት ያነበበውን ቃላቶቹንም
በእዘን ሥጋ በእዝነ ልቡና የሰማውን የሕጻን ቂርቆስ
የከበሩ ጣቶቹ በብርሃን ክርስቶስ ሥልጣን በአንድነት ይባርኩን፡፡

እነሆ ከገድሉ አውጥቼ የቂርቆስንና
የወገኑ የኢየሉጣን መልክዕ ጻፍሁ፡ የሁሉ እመቤት
ማርያም ሆይ! ባርኪልኝ፡ በምድር የባረክሽው በሰማይ
የተባረከ ነውና የቀደስሽውም ለዘላለም ይኖራልና፡፡

መባርትትና ነጎድጓድን የምትይዝ ሆይ! እሳቱን ስላቀዘቀዘ
ስለ ሕጻኑ ኪዳን ከቸነፈር ታደገን፡ ይህችንም ዐጸድ
ከመራራ ቸነፈር ታድናት ዘንድ በምስክርነት ደሙ ተማጽነናል፡፡

ፊተኛውና ኋለኛው /አልፋና ዖ/ ሆይ! ቂርቆስን
በጠራነው ጊዜ በደለኛውን አውሬ እናቸንፈው
ዘንድ በምስክርነት ደሙ ተማጽነናል ቤትህ ከተሠ
ራበት ቸነፈር አይምጣ ብለህ ቃል ገብተህለታልና
ከቸነፈር ፍላጻ እንድንድን አቤቱ ደግፈን፡፡

ሕጻንና እናቱ ሁለቱም ገድላቸውን ፈጸሙ፡
የጋኑ ድምፅ እንደክረምት ነጐድጓድ ነበር፡ የከበሩ
ሰማዕት ግን ሞትን አልፈሩትም፡፡

የኢየሉጣ ልጅ ብፁዕ ቂርቆስ ወደ እቶኑ (ጋኑ)
ለመግባት አልፈራም፤ ጌታም ቤትህን በጽኑ እምነት
ከሚሠራ ሰው ችነፈርን አስወግዳለሁ ብሎ
የምሕረት ኪዳን ሰጠው።

እካለ መጠን ያላደረስህ ቂርቆስ ሆይ ከጓደኛህ
ከሚናስ ጋር ሰላም እልሀለሁ፤የዮናስ ቅል በሌሊት
በቅላ ከዋዕየ ፀሐይ ግለት እንደጋረዳቸው
በደመና ረድኤትህ ዘወትር ጋርደኝ።

የቅዱስ ቂርቆስ የእናቱም የኢየሉጣ አምላክ ሆይ
አገልጋይህ ________________ ን ከጥፋት ዘመን ከክፉም
ቀን ጠብቀኝ እድነኝም ሠውረኝ ታደገኝም።

የከሀዲዎች ቁጣ ወደእቶን ለመግባት ያላስፈራህ
መልክህና ደምግባትህ ያማረ ሕጻን ቂርቆስ ሆይ
ሰላም ላንተ ይሁን።

ተአምርህ የከንፈሮች ቃል የነገርም መብዛት የማይፈጽመው
ከባሕር አሸዋና ከማር ይልቅ የበዛ ነው ሰላም ላንተ ይሁን!

ሥራህን እስኪያደንቁ ድረስ
በእስክንድርስ አደባባይ ሜማጡን በሬ ያደረግህ
ከእንንቱም ፍየልን ያወጣህ ሆይ ሰላም ላንተ ይሁን።

ስምህ ያማረ ቂርቆስ ሆይ ውኃ ቀለም
ሆኖ ቢጻፍ እንኳ ዓለም ተአምርህን ባልቻለው
ነበር፣ሰላም ላንተ ይሁን።

ቂርቆስ ሆይ ጥቂት እጅመንሻ ስላቀረብሁልህ
ፊንታ በደስታ አደባባይ እቆም ዘንድ የመጋደልህን
ዋጋ አብዝተህ አሰጠኝ።

ቂርቆስ ሆይ ሰላም ላንተ ይሁን
በምቆምበት ጊዜ በየሰዓቱ በወልድና
በእናቱ ፊት የዚህ ምልጃዬ መልእክተኛ ነህ በለኝ።
ሰላም ላንተ።

ተከዚን የምትተካከል የሰላማችን ወንዝ
ቂርቆስ ሆይ ከሕዝባችን ልብ ማጣትን ታስ
ወግድ ዘንድ በየጊዜው ለመባረክና
ለማረጋጋት ና ና።

---------------------------- // ----------------------------

ቅዱስ የሆነ የእግዚአብሔር ምስጋናውን
ስለኢየሱስ ክርስቶስ አስቀድማለሁ
ዳግመኛም አዲስ የሚሆን የኢየሉጣን ዜና አስከትላለሁ
ሥጋና ነፍስን የሚያስጥም የውዳሴዋ ፍቅር
በላዩ ፈስሷልና።

ለሰው ሁሉ አፍ እንደማር ለጣፈጠ የስምሽ መታሰቢያ
ሰላምታ ይገባል። እናታችን ኢየሉጣ ሆይ ያላንቺ እናት
የላቸውምና የዚህችን ገዳም ልጆች ከ (ቅድስት) ማርያም
ጋር በየቀኑ ጎብኚ።

ለራስ ፀጉርሽና የሚያበራ የብርሃን አክሊልን
ለተቀዳጀ ራስሽ ሰላምታ ይግባል።
ኢየሉጣ ሆይ ሀብትሽ የምድርን ድሆች ባለጠጋ አደረገ
የረድኤትሽ አውሎ ከሀብቱ ቃል የተነሣ በረታ፣
ችግረኞችንም እንዳያይ ቃል ገባ።

እንደ መስፍን ሙሴ ፊት ብርሃን ለሚከበው ፊትሽ
ሰላምታ ይገባል ማኅፀንሽ የተባረከ ኢየሉጣ ሆይ ወይን
ውዳሴሽን በምንጠጣው ጊዜ ኀዘን ከልባችን ይወገዳል።

ለቅንድቦችሽ የመኳንንቱንና የወታደሮችን ማስፈራራት ላዩም
ዓይኖችሽ ሰላምታ ይገባል የከበሩ ሴቶች ርብቃና ሣራ እንዳንቺ
ወደምስክርነት አደባባይ አልሔዱም የብርሃን ዘውድም
አልተቀዳጁም።

የጠላትን ምክር ሳልሰሙ ጆሮዎችሽ በመከ[illegible]ንም
እጅ በጥፊ ለተመቱ ጉንጮችሽ ሰላምታ ይገባል
ኢየሉጣ ሆይ! ሰማያዊ ሙሽራ ወደ አደራሽ በገባ ጊዜ
ከእምነቱ ደናግል ጋር በውጭ እንዳልቆም ከዘይትሽ ዘይት ስጪኝ

ሹቱን ሳሸተቱ አፍንጮሽ ሞገስም ከእነርሱ ለፈሰሰ
ከንፈሮችሽ ሰላምታ ይገባል::
ኢየሉጣ ሆይ ዳዊት ልጅሽ /ቂርቆስ/ ንጉሥ ደም ግባትሽን ወድዷልና ሐሰተኛ
የልብ ጥርጥር መገንሽን እርሺ ብሎ ተናገረ /ሽ/

ለመድኃኒታችን ለተገዛ አፍሽ /አንደበትሽ/ ንጻታቸውም ለሚያ
ምር ጥርሶችሽ ሰላምታ ይገባል::
ኢየሉጣ ሆይ! እንደ ተጋዳይ አርሳኒ ዝም አላልሁም እንደ
ጳውሎስም የገዥ የአብን ሕግ አልተናገርሁምና መጋደልሽ
የልብና ተስፋ ይሁነኝ::

ለምላስሽና ለሚሰማው ሰው ጣፋጭ ለሆነ ቃልሽ
ሰላምታ ይገባል::
በሚያስፈራ የፍርድ ቀን ጻድቃን በገደል ሰማታትም
በደም ተስፋ ሲያደርጉ ኢየሉጣ ሆይ እኔም ፍጹም
በሆነ ቃልኪዳንሽ ተስፋ አደርጋለሁ::

ለትንፋሽሽ ጣፋጭና መራራን ለሚለይ ድንቅ ጉሮሮሽም
ሰላምታ ይገባል
ኢየሉጣ ሆይ ወደ ሰማያዊት ሀገር ምሪኝ
የጸጋና የክብር ብርሃን ካልመራኝስ እንደሙሽራው
አብርሃም ምግባር የለኝም::

ሰይፍ የወርቅ ማርዳን ላሰረ አንገትሽ፣ በአንገት ደም ለተነከረ ትከሻሽም ሰላምታ ይገባል፡
ኢየሉጣ ሆይ ጽድቅሽ በሁሉ ዘንድ ታወቀ
በስምንተኛው ዘመን ቸር አልቋልና መሣለቂያ
እንዳልሆን ከጠላቶቼ ታደጊኝ።

ለጆርባሽ የዕውቀትና የጥበብ ማረፊያ ለሆነ መዝገብ
ደረትሽም ሰላምታ ይገባል
እናታችን ኢየሉጣ ሆይ
ሕዝብ ልጆችሽን መመገብ ትወጂያለሽ በቀረበ ዘመንም
ቤትን መተውም የለብሽምናበርግብ እንመስልሻለን።

የሕጻን ቂርቆስ መቀመጫ ለሆነ እቅፍሽ ለታሠሩ
እጆችሽም ሰላምታ ይገባል
ስምሽን ለጠራ ችግረኛ ኢየሉጣ መጽናኛ ኢየሉጣ መጠጊያ
ኢየሉጣ ምግብ ኢየሉጣ ልብስ ነሽ።

በርኅራኄና በይቅርታ ቃል ለወርቆችሽ እና ለክርንሽ ሰላም
እላለሁ፣ ኢየሉጣ ሆይ ወንጌል ጽድቅሽን እያሳሰበች በሥቃይና
በገድል ዘመን ብዙዎችን ወሰድሁ ነገር ግን እንደ ኢየሉጣ
ያለች አልወሰድሁም ትላለች።

በምልጃና በጸሎት ጊዜ ለተዘረጉ ክንድሽና
መዳፎችሽ ሰላምታ ይገባል
ኢየሉጣ ሆይ የሚያስፈራ እሳትን መፍራትሽ አይደንቅብሽም
ጴጥሮስ እንኳ የአንዲትን ሴት ቃል በሰማ ጊዜ እሳት
ሳያይ ፍርሀት ያዘው።

ለዐሥሩ ጣቶችሽና በነርሱ ላይ ላሉ ጥፍሮች /ሽ/
ሰላም እላለሁ፣ የእግዚብሔር ማደሪያው የተመረጥሽ
ኢየሉጣ ሆይ የጠላቶች ሁከት ውኃ ፍቅር ቤትሽን
ማጥፋት አይችልም።

እንደ ሁለት የጥንቸል ግልገሎች ለሆኑ ጡቶችሽ
በሚያበራ የወርቅ ሐመልማል ሳጌጠ ጎንሽም ሰላምታ ይገባል
ኢየሱጣ ሆይ! የወንጌል ልጆች ኢየሱጣና ኃያል ቂርቆስ
ከእኛ ጋር ሳሉ እኛን ማኘት ነፍ የሚችል የለም ይላሉ፡፡

ለሆድሽና እንደ የዋህ ሙሴ ልብ ለሚራራ ልብሽ
ሰላምታ ይገባል እናታችን ኢየሱጣ ሆይ በመከራና
በልቅሶ ዘመን ኖኅ ርግብን ወደ ውኃ እንደላካት
አስተማሪ ልጅሽን ወደኛ ላኪው፡፡

መከራ የመቀበልን ዜና ለሰማ ኩላሊትሽና የኃጢአት
አሳብን ላቸነፈ ጎሊናሽ ሰላምታ ይገባል
የምትራዳ ኢየሱጣ ሆይ ከሚራዳን ልጅሽ ጋር
በሞቴ ሰዓት ነይ/ልኝ/ ያን ጊዜ ዓይኔ አንቺን ያያልና፡፡

በኀዘን ለተቆረጠ አንጀትሽ ከውጫዊ አካል ይልቅ
ለክብረ ሆድዕቃሽም ሰላምታ ይገባል
ወደ ሰማያዊት ሀገር የገባሽ ኢየሱጣ ሆይ
ያከበረሽ ይከብራል ያዋረደሽም ይዋረዳል፡፡

የብር ቀፋ ክርስ ጋር ላለ እንብርትሽ ሰላምታ ይገባል
ለተባረከ ማኅፀንሽም ዳግመኛ ሰላም ይሁን
በአንድነታችን ውስጥ ክርክር እንዳይሆን በየቀኑ
ይቅር ባይ ወደ ሆነ አምላክ ለምኚ፡፡

ንጽህናን ለታጠቀ ወገብሽ እንደ ምሰሶዎች ለጸኑ
ጭኖችሽም ሰላምታ ይገባል ኢየሱጣ ሆይ ከፍያልሽ ነሽ
ኢየሱጣ ሆይ እንደ ደመና ነሽ ሐና በልጇ ተስፋ እንዳደረገች
በወለድሽው ልጅሽ ልዕልና ተስፋ ልታደርጊ ይገባሻል፡፡

# መልክአ ኢየሉጣ

ለጉልበቶችሽና ቅንዐትንና እስፈሪነትን በተመላ ከሀዲ መኰንን
ፊት ለቆሙ እግሮችሽ ሰላምታ ይገባል
እርሴማ ድካሚን በኃይል ለውጣ የሚጣላትን ንጉሥን እንደቸነፈችው
ኢየሉጣ ሆይ አንቺም ያቸነፍሽ ሰይጣንን አቸነፍሽው።

በወንጌላዊት አዳራሽ ውስጥ ለተመላለሱ
ለተረከዝሽና ውስጥ እግሮች ሰላምታ ይገባል
ከስድሳ ንግሥታት መካከል የተመረጥሽ ኢየሉጣ ሆይ
አቢሳ ዳዊትን እንደጠበቀው ልጅሽ ከልብ ጥርጥር አንበሳ ጠበቀሽ።

ለጣቶችሽና በአሥሩ ቃላት ቁጥር ልክ ለተቆጠሩ ጥፍሮችሽ
ሰላምታ ይገባልየሰማዕታት እናታቸው ኢየሉጣ ሆይ ጸጋሽ
ከፍጥረት ሁሉ ይልቅ በበዛ ጊዜ ሴቶች በእናታችን (በራሳችን)
ላይ ትቀመጥ አለ።

ዘንባባን ለሚመስል ቁመናሽ ለመልኮችሽም ሁሉ
ጥቂት ሳንለይ ሰላምታ ይገባል
ኢየሉጣ ሆይ መሥዋዕት ትሆኚ ዘንድ ወደድሽ
የዮፍታሔ ልጅ ግን ብፅዓትን ልትፈጽም
ያስፈቃዷ ተሠዋች ሞትንም ተቀበለች።

በከሀዲ መኰንን ሰይፍ
ለነፍስሽ ከምድራዊ የሥጋ እንቀጽ መውጣት ሰላምታ ይገባል
ብቸኛዋ ኤልያስ ወደገነት ሲያርግ ለኤልሳዕ
በእጥፍ እንደሰጠው ኢየሉጣ ሆይ! ጸጋሽን በላያችን ላይ አፍስሺ።

የእምነት ሙዳይ እናታችን ኢየሉጣ ሆይ እንደ ሹቱ ለሚጣፍጥ
በድን ሥጋሽ ሰላምታ ይገባል እንደተመረጠ ልጅሽ ሠረገላም ቢኖር
እንደኔም የተቆፈረ መቃብር ቢኖር እኔ በደለኛ የሥጋሽን ሥፍራ
አላውቅሁትም።

ለአብ ምስጋና ይገባል ለወልድም ምስጋና ይገባል
ለመንፈስ ቅዱስም ምስጋና ይገባል
ይህን ምስጋና ለመናገር እንቃቅተውኛልና
አቤቱ ከተመረጠች ኢየሉጣ ጋር ዋጋዬን ልካፈል
ለሚያገለግል ዋጋ ይገባዋልና።

እናቴ ኢየሉጣ ሆይ ሰላም ላንቺ ይሁን ኢየሉጣ
ጠዳጅ ኢየሉጣ አረጋጊዬ ነሽ።

የወልድሽው ሕጻን አባት ሆነሽ
የሃይማኖትንም ሕግ አስተማረሽ ሰላም ላንቺ።

ኢየሉጣ ሆይ ሰላም ላንቺ ይሁን የደከመች ማርታ ያልደከ
መችም ማርያም፣ ልጆቿንም ለሰማዕትነት የሰጠች ሶፍያ ካንቺ
ጋር አይተካከሉም።

እናታችን ኢየሉጣ ሆይ ሰላም ላንቺ ይሁን የሰማይ መላእክት
ከታናሽነትሽ ጀምሮ የተባረክሽ ነሽ ልጅሽም የተባረከ ነው ይሉሻል
ኢየሉጣ ሆይ ኃጢአተኛ አገልጋይሽን ለመርዳት ድረሺ።

ሰላም እላለሁ ኢየሉጣ ሆይ ትጊ፣ ጠላቴ ጥርሶቹን
ሲያፋጭ ከእኔ አትራቂ።

ሰላም ላንቺ ከልጅሽ ጋር በብዙ ዘለፋ አደባባይ
ቆምሽ፣ ኤልሳቤጥ ግን ልጇን አቅፋ በዚፋ በረሀ ተሸሸገች

ኢየሉጣ ሆይ ሰላም ላንቺ ይሁን ፍርድን በማሰብ ስለምን
ትፈራለህ ታዝናለህስ? ከአምላክ ኪዳን የተቀበልሁት
አንተን አማልዶ ዘንድ አይደለምን በዬኝ።



የመጽሐፉ ተርጓሚ መምህር ጎሩይ ኤርምያስ

<u>በተርጓሚው የተጻፉ</u>

<u>ድርሰት</u>

- መዝገበ ታሪክ ክፍል ፩
- መዝገበ ታሪክ ክፍል ፪
- መልካም ዜጋ ማን ነው?

<u>ትርጉም</u>

- Daily Prayer (የዘውትር ጸሎት)
- ገድለ ቂርቆስ ወኢየሉጣ